ለአብዮታዊ ውይይት መነሻ

፮

# የሌኒኒዝም መሠረታዊ ትምህርቶች

ለአብዮታዊ ውይይት መነሻ

6

# የሌኒኒዝም መሠረታዊ ትምህርቶች

የሕዝብ ድርጅት ጉዳይ ጊዜያዊ ጽ/ቤት
የፍልስፍና ማስፋፊያ የትምህርትና ፤ ማስታወቂያ ኰሚቴ
የካቲት ፲፱፻፸፱
አዲስ አበባ

# ማ ው ጫ

# ማስታወሻ

ሌኒን በ፲፱፻፳፬ ዓ. ም. ሲያርፍ ጆሴፍ ስታሊን የፓርቲውን የመሪነት ሥልጣን ተረከበ ። ስታሊን ለሌኒን መርሆዎች አሸናፊነት ቁርጠኛ ታጋይ ነበርና በፓርቲው ውስጥ በነትሮትስኪና ጓዶቹ ተነስቶ የነበረውን ፀረ ሌኒኒስት አቋም ለመደምሰስ ቆርጦ ተነሳ ። የሌኒኒዝም መሠረታዊ ትምህርቶች በሚል አርእስት በተከታታይ በስቬርድሎቭ ዩኒቨርስቲ ለሌኒን ፓርቲ ተመዝጋቢዎች ያደረገው ንግግር የዚህ ተጋድሎው ቋሚ ምስክር ነው ።

ይህ ንግግሩ በሚያዝያና ግንቦት ወሮች ፲፱፻፳፬ ዓ. ም. በመጽሐፍ መልክ ተዘጋጅቶ ወጣ ። ስታሊን በዚህ ጽሁፉ በሌኒን ተዘጋጅቶ በሶስተኛው ዓለም አቀፍ ኮሚኒስት ኮንግረስ ላይ የፀደቀውን የወዝአደሩ ፓርቲ ድርጅታዊ መርሆዎች አጠር ባለ ፤ በተቀላጠፈና ግልጽ በሆነ መንገድ ከማብራራቱም በላይ ስለሌኒኒዝም ምንነት ፤ ስለዘዴው ፤ ስለቲዮሪው ፤ ስለወዝአደሩ አምባገነንነትና ፤ ስለገበሬው ጥያቄ ፤ ስለብሔር ጥያቄ ፤ ስለ ስትራቴጅና ታክቲኩ ፤ ስለፓርቲው ድርጅታዊ መዋቅር ፤ ባጠቃላይ ሌኒን ይቆምላቸው የነበሩትን መርሆዎች በሚገባ አብራርቷል ።

ስታሊን ያቆየን ይህ ትምህርት ዛሬ በመላው ዓለም ለሚገኙ ሀቀኛ ማርክሲስት ሌኒኒስቶች መመሪያ ቸው ከመሆኑም በላይ ከሌኒን ሞት በኋላ ሌኒኒዝም በታሪክ ትክክለኛ ሥፍራውን እንዲይዝ ከረዱት ማርክሳዊ ጽሁፎች አንደኛው ነው ። እንዲያውም ማርክሲዝም ሌኒኒዝምን ለማስተማር መመሪያ እንዲሆን ሶስ

ተኛው ኢንተርናሽናል ከነደፈው ፕሮግራም ውስጥ የሌኒኒዝም መሠረታዊ ትምህርቶች አንደኛው ነው ።

ይህንን ጽሁፍ አብዮታዊት ኢትዮጵያ ጋዜጣ “ለጥ ናት ክበቦች” በተሰኘው አምዱዋ አጠር ባለ መልክ በተከታታይ አቅርባ እንደነበር የሚታወስ ነው ። ሆኖም አጠቃሎ ማቅረቡ ጽሁፉ የሶሻሊዝም ቲዮሪን ለማዳበር በጣም ጠቃሚ ስለሆነ በተለይ ለውይይት ክበብ ጓዶች እንዲያመች በማሰብ ሰፋ ባለ መንገድ ተተርጉሞ በአንድ ጥራዝ እንዲታተም ተደርጓል ።

የሌኒኒዝም መሠረታዊ ትምህርቶች በሚተረጎም በት ጊዜ ትርጉሙ የተሟላ እንዲሆን አስፈላጊው ጥንቃቄ ተደርጓል ። ሆኖም ትርጉሙ ፍጹም ነው ለማለት ስለ ማንደፍር አንባቢያን የሚጠቁሙልንን ስህተቶች ለማረም ዝግጁ ነን ።

ለወደፊቱም ለሰፊው ህዝብና በተለይም ለጥናት ክበብ ጓዶች የሚያገለግሉ ጽሁፎች በዚህ መጽሔት መልክ ለማቅረብ ያቀድን ስለሆነ አንባቢያን ያላቸውን አስተያየት ለሕዝብ ድርጅት ጉዳይ ጊዜያዊ ጽ/ቤት የፍልስፍና ማስፋፊያና የማስታወቂያ ኮሚቴ የመልእ ክት ማጥን ቁጥር ፲፱፻፸፱ አዲስ አበባ ቢልኩልን በደስታ እንቀበላለን ።



# የሌኒኒዝም መሠረታዊ ትምህርቶች

የሌኒኒዝም መሠረታዊ ትምህርቶች ትልቅ ርእስ ነው ። በሰፊው ለመተንተንም አንድ ሙሉ ቅጽ ይፈል ጋል ። እንዲያውም ከአንድ በላይ ቅጾች ያስፈልጋሉ ። ስለዚህ የኔ ንግግር ሁሉንም የሚያዳርስ የሌኒኒዝም ገለጻ ሊሆን አይችልም ። ሊሆን ቢችል አጠር ያለ የሌኒኒዝም መሰረታዊ ትምህርቶች ጭምቅ ሃሳብ (ሲኖፕሲስ) ነው። ያም ሆነ ይህ ለተሟላ የሌኒኒዝም ጥናት መንደርደርያ የሚሆኑ አንዳንድ መሠረታዊ ነጥቦች ለማስቀመጥ ይህ ንን አጠር ያለ ጭምቅ ሃሳብ መስጠቱን ጠቃሚ አድርጌ እገምታለሁ ።

የሌኒኒዝምን መሰረታዊ ትምህርቶች ማብራራት ማለት የሌኒንን ርእዮተ ዓለም መሰረት ማብራራት ማለት አይደለም ። የሌኒን ርእዮተ ዓለምና የሌኒኒዝም መሰረታዊ ትምህርቶች ልዩነት የሌላቸውና በአመለካ ከትም (ስኮፕ) ፍጹም አንድ የሆኑ አይደሉም ። ሌኒን ማርክሳዊ ነበር ። ማርክሳዊነትም የርእዮተ ዓለሙ መሰ ረት ነበር ። ከዚህ ተነስቶ ሌኒኒዝምን ለመግለጽ ወይንም ለማብራራት የማርክሲዝምን መሰረታዊ ትምህርቶች ከማብራራት መጀመር ያስፈልጋል ለማለት አይቻልም ። ሌኒኒዝምን ማብራራት ማለት በሌኒን ሥራዎች ውስጥ አዲስና ልዩ የሆኑትን ፤ ለጠቅላላው ማርክሲዝም መዳበር እሱ ያበረከተውንና ከእሱ ስም ጋር የተያያዘውን ማብ ራራት ማለት ነው ። በንግግሬም ውስጥ ስለሌኒኒዝም መሰረታዊ ትምህርቶች የምናገረው በዚህ መንፈስ ነው ።

## እንግዲያው ሌኒኒዝም ምንድን ነው?

አንዳንድ ሰዎች ሌኒኒዝም ማለት ልዩ በሆነው በሩሲያ ሁኔታ ላይ ማርክሲዝምን በተግባር ላይ ማዋል ማለት ነው ይላሉ ። ይህ አባባል ጥቂት እውነትን ያዘለ ቢሆንም በምንም ዓይነት አጠቃላዩን እውነት አልያዘም ። እርግጥ ሌኒን እንከን በማይወጣለት አኳኋን ማርክሲዝምን በሩሲያ ሁኔታ ላይ አውሏል ። ይሁን እንጂ ሌኒኒዝም ማለት ማርክሲዝምን በተለይ ለሩሲያ ብቻ በሆነው ሁኔታ ማዋል ነው ከተባለ ሌኒኒዝም ብሔራዊና የሩሲያ ብቻ ክስተት ይሆናል ። ነገር ግን ሌኒኒዝም የሩሲያ ብቻ ሳይሆን በጠቅላላው የዓለም እድገት ውስጥ የተመሰረተ ዓለም አቀፍ ክስተት መሆኑን እናውቃለን ። ስለዚህ ነው ይህ አባባል አንዱን ገጽ ብቻ የሚመለከት ቁንጽል ነው ብዬ የምገምተው ።

ሌሎች ደግሞ ሌኒኒዝም በአስራ ዘጠነኛው ምእተ ዓመት ማለትም በ፲፰፻፵፰ ዓ. ም. ገደማ የነበረው አብዮታዊ ማርክሲዝም እንደገና ማንሰራራት ነው ይላሉ ። ይህም አባባል ከ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ገደማ በኋላ ማርክሲዝም የለዘበና አብዮታዊ ያልሆነ ተብሎ ከሚታሰብበት ለመለየት ነው ። ይህንን የማርክስን ትምህርት አብዮታዊና ለዘብተኛ ብሎ በሁለት ቦታ የሚከፍል ተራ የሆነ አባባል ቸል ብንለው ይህ ፍጹም በቂ ያልሆነና የማያጠግብ አባባል ቅንጣት የምታህል እውነት እንኳ እንዳዘለ ማመን ይኖርብናል ። ይህችን ቅንጣት እውነት ብንወስድ እውነትም ሌኒን በሁለተኛው ኢንተርናሽናል አድርባይነት ታፍኖ የነበረውን የማርክሲዝምን አብዮታዊ ይዘት ወደቦታው መልሶታል ። ግን አሁንም ቢሆን ይህ የእውነቱ በጣም አነስተኛ ክፍል ነው ። የሌኒኒዝም የተሟላው እውነት ግን ሌኒኒዝም ማርክሲዝምን እቦታው መመለሱ



ብቻ ሳይሆን ማርክሲዝምን በአዲሱ የካፒታሊዝም ሁኔታና የወዝአደሩን የመደብ ትግል ለማዳበር አንድ እርምጃ ወደፊት ማራመዱ ነው ።

## ታዲያ ሌኒኒዝም ምንድን ነው?

ሌኒኒዝም የዘመነ ኢምፔሪያሊዝምና የወዝአደሩ አብዮት ማርክሲዝም ነው ። ይበልጥ ጥርት አድርጎ ለመናገር ሌኒኒዝም ባጠቃላይ የወዝአደሩ አብዮት ቲዮሪና ታክቲኮች በተለይም የወዝአደሩ የበላይ ገዢነት ቲዮሪና ታክቲኮች ነው ። ማርክስና ኤንግልስ አብዮታዊ ትምህርታቸውን ያካሄዱ የነበሩት የዳበረ ኢምፔሪያሊዝም ገና ባልነበረበት ጊዜ ፤ ወዝአደሮች ገና ለአብዮት በሚዘጋጁበት ጊዜ ፤ የወዝአደሩ አብዮት ወዲያውኑ በተግባር ሊገለጽ ገና አመቺ ባልሆነበት ጊዜ ነበር ። የማርክስና የኤንግልስ ደቀመዝሙር የነበረው ሌኒን ግን ድርጊቶቹን ያካሄድ የነበረው ኢምፔሪያሊዝም በዳበረበት ዘመን ፤ ወዝአደራዊ አብዮት መገለጥ በያዘበት ፤ ወዝአደራዊ አብዮት ከአሁኑ በአንድ ሀገር አሸናፊ በሆነበት ፤ የቡርዧ ዲሞክራሲን በሰባበረበትና የወዝአደሩን ዲሞክራሲ ዘመን ፤ የሶቪዬቶችን ዘመን ባሳየበት ጊዜ ነበር ።

ሌኒኒዝም ማርክሲዝምን በይበልጥ አዳብሯል የተባለውም ስለዚህ ነው ።

የሌኒኒዝምን በጣም ልዩ የሆነ አብዮታዊ ባህርይ መጥቀስ የተለመደና ትክክልም ነው ። ይህ የሌኒኒዝም የተለየ ባህርይ ከሁለት ምክንያቶች የመነጨ ነው ። አንደኛ ከወዝአደራዊ አብዮት አብራክ በመውጣት የሱን መልክ መያዙ ሲሆን ፤ ሁለተኛ ፤ ከሁለተኛው ኢንተርና

ሽናል አድርባይነት ጋር እየታገለ ማደጉ ነው ። ይህም ትግል ከካፒታሊዝም ጋር ለሚደረገው ትንንቅ መሳካት የግዴታ አስፈላጊ የነበረና አሁንም ተቀዳሚ የሆነ ተግባር ነው ። በማርክስና ኤንግልስ ዘመንና በሌኒን ዘመን መሀከል የሁለተኛው ኢንተርናሽናል አድርባይነት ተጋሪ ያልነበረው የበላይነትን አሳይቶ ስለነበር ይህንንም አድርባይነት በመቃወም የተደረገው ርሀራሄ የሌለው ትግል ከሌኒን እጅግ ታላላቅ ተግባሮች ውስጥ አንዱ እንደነበረ መረሳት የለበትም ።

## ፩. የሌኒንዝም ታሪካዊ መሠረቶች

ሌኒኒዝም ያደገውና መልክ የያዘው በኢምፔሪያሊዝም ሁኔታዎች ስር ነው ። ይህም የካፒታሊዝም ቅራኔዎች እጅግ የከረረ ደረጃ ላይ በደረሱበት ፤ ወዝአደራዊ አብዮት አጣዳፊ ተግባራዊ ጥያቄ በሆነበት የሠራተኛውን መደብ ለአብዮቱ የማዘጋጀቱ ጊዜ ተፋፍሞ ካፒታሊዝምን ወደ መዋጋት ደረጃ የተሸጋገረበት ጊዜ ነበር ።

ሌኒን ኢምፔሪያሊዝምን “በጣር ላይ ያለ ካፒታሊዝም” ብሎታል ። ምክንያቱም ኢምፔሪያሊዝም የካፒታሊዝምን ቅራኔዎች እስከ መጨረሻው ክልላቸው ገፍቶ አብዮት ወደሚጀምርበት ደረጃ ስለሚያደርሳቸው ነው ። ከእነዚህ ውስጥ በግምባር ቀደምትነት የሚታሰቡ ሶስት ቅራኔዎች አሉ ።

የመጀመሪያው ቅራኔ በወዝና (ስራ) በካፒታል መሀከል ያለው ቅራኔ ነው ። ኢምፔሪያሊዝም ፤ ኢንዱስትሪ በዳበረባቸው ሀገሮች የሞኖፖሊስት ትረስቶችና የሴንዲኬቶች ፤ የባንኮችና የጥቂት ባለገንዘቦች ወሰን የሌለው ሀያልነት (ኦምኒፖተንስ) ነው ። ከዚህ ወሰን



የለሽ ሀያልነት ጋር ለሚደረገው ትግል የሰራተኛው መደብ የተለመዱ የትግል ዘዴዎች ማለትም የሙያ ማህበሮችና የላሉ የህብረት ድርጅቶች ፤ ፓርላማዊ ፓርቲዎችና በፓርላማ አማካይነት የሚደረገው ግብግብ በፍጹም በቂ አለመሆናቸው ተረጋግጦአል ። ኢምፔሪያሊዝም በሰፊው ወዝአደር ፊት ሁለት አማራጭ መንገድ ያስቀምጣል ። አንድም እንዳደረግህ አድርገኝ ብሎ ራስን አሳልፎ ለካፒታል በመስጠት የተለመደውን ጎስቋላ የሆነ ከቀን ወደ ቀን ወደታች እያሽቆለቆለና እየሰመጠ ለሚሄድ ኑሮ መጋለጥ ፤ አለያም በአዲስ የትግል መሳሪያ በመጠቀም ጭቆናን አሽቀንጥሮ መጣል ናቸው ። በዚህም አማራጭ ኢምፔሪያሊዝም የሰራተኛውን መደብ ወደ አብዮት ይመራዋል ።

ሁለተኛው ቅራኔ ፤ ልዩ ልዩ የባለገንዘብ ድርጅቶችና የኢምፔሪያሊስት ሀይሎች ጥሬ ዕቃዎችን ለማግኘት ሲሉ በሌሎች አገሮች ላይ በሚያካሄዱት የግዛት ማስፋፋት ዘመቻ በመሀከላቸው የሚነሳው ቅራኔ ነው ። የኢምፔሪያሊዝም አንዱ ጠባይ ምርትን (ካፒታልን) ጥሬ ዕቃዎች ወደሚገኙበት ስፍራ በመውሰድ የጥሬ ዕቃዎች ምንጭ የሆኑትን ሁሉ በግል (በሞኖፖል) ለመያዝ በነዚህ ሀይሎች መሀከል የሚደረገው እብደት የተቀላቀለበት ትግል ነው ። የዚህም ትግል ዓይነተኛ መልኩ አዲስ የመጡ የባለገንዘብ ድርጅቶችና ሀይሎች ከነሱ ቀድመው በነበሩት ሀይሎች ላይ በሚሰነዝሩት ትግል ፤ አሮጌዎቹ የያዙትን ላለመልቀቅ ፤ አዲሶቹም አስለቅቀው “ድርሻቸውን” ለመያዝ ሕሊናቸውን እስኪስቱ ድረስ ቀድሞውኑ የተከፋፈለውን ዓለም እንደገና ለመከፋፈል የሚያደርጉት ግብግብ ነው ። ይህ በልዩ ልዩ የካፒታሊስት ቡድኖች መሀከል የሚደረገው እብደት

የተቀላቀለበት ትግል በኢምፔሪያሊዝም ማህፀን ውስጥ ለግዛት ማስፋፋት የሚደረጉ ጦርነቶችን አጠራቅሞ ይዞአል ። ይህ ጥርቅም ደግሞ በተራው እርስ በርስ የሚፋተጉት የኢምፔሪያሊስት ሀይሎች እንዲዳከሙ አድርጎ የካፒታሊዝምን ቅስም በማንኮታኮት የወዝአደሩን አብዮት ዋዜማ እያበሰረ ወደ አብዮቱ ማእበል ይመራዋል ።

ሶስተኛው ቅራኔ ደግሞ እፍኝ በማይሞሉ "የሰለጠኑ" አገሮችና በብዙ መቶ ሚሊዮን በሚቆጠሩ ጥገኛና ቅኝ የሆኑ የአለም ሕዝቦች መሀከል ያለው ቅራኔ ነው ። ኢምፔሪያሊዝም ጥገኛና ቅኝ ግዛት በሆኑ ሀገሮች ውስጥ በሚኖሩ በብዙ ሚሊዮን በሚቆጠሩ ሕዝቦች ላይ የሚያካሂደው ፍጹም ሐፍረተ ቢስ ብዝበዛና እጅግ ኢሰብአዊ የሆነ ጭቆና ነው ። የዚህ ብዝበዛና የዚህ ጭቆና አላማ እጅግ ከፍተኛ የሆነ ትርፍ መጭመቅ ነው ። ነገር ግን እነዚህን ሀገሮች ሲበዘብዝ ኢምፔሪያሊዝም በነዚህ ሀገሮች የባቡር ሀዲዶችን ፣ ፋብሪካዎችን፣ የኢንዱስትሪና የንግድ ሥፍራዎችን ለማቋቋም ይገደዳል ። በነዚህ ተበዝባዥ ሀገሮች የወዝአደሩ መደብ መታየት ፣ የሀገሩ ምሁራን ብቅ ማለት ፣ የብሄራዊ ንቃተ ህሊና መነሣሣትና የነፃ አውጪዎች እንቅስቃሴ ማደግ ከኢምፔሪያሊዝም "መመሪያ" አብራክ የሚወለዱና የማይቀሩ ውጤቶች ናቸው ። ጥገኛና ቅኝ ግዛት በሆኑት ሀገሮች በመላ የአብዮታዊ እንቅስቃሴ እድገት በግልጽ የሚያረጋግጠው ይህንን ሀቅ ነው ። ይህ ሁኔታ ለወዝአደሩ እጅግ ጠቃሚ ነው ። ምክንያቱም ጥገኛና ቅኝ ግዛት የሆኑትን አገሮች ከኢምፔሪያሊዝም ደጀንነት ወደ ወዝአደሩ አብዮት ደጀንነት በመለወጥ ስር ነቀል በሆነ ሁናቴ ካፒታሊዝምን ስለሚያመነምነው ነው ።



ባጠቃላይ የድሮውን "ታዳጊ" ካፒታሊዝም በጣር ላይ ወዳለ ካፒታሊዝም የለወጡት ዋና ዋና ቅራኔዎች እነዚህ ናቸው ።

ከአስር አመታት በፊት ለተነሳው የኢምፔሪያሊስቶች ጦርነት ልዩ ግምት የሚያሰጠው እነዚህን ሁሉ ቅራኔዎች አንድ ላይ ቶርቦ እንዲመዝን በማድረግና ወዲያውኑም የወዝአደሩን አብዮታዊ ጦርነቶች ማፋጠኑ ነው ። በሌላ አነጋገር ኢምፔሪያሊዝም የአብዮቱን በተግባር መዋል የማይቀር ብቻ አላደረገውም ፤ በካፒታሊዝም የመጨረሻ ምሽግ ላይ በቀጥታ ለሚደረገው ውጊያ ምቹ ሁኔታዎችንም ፈጥሯል ።

ሌኒኒዝምን የፈጠረው አለም አቀፍ ሁኔታ ይህ ነበር ።

ይህ ሁሉ ጥሩ ነው ይባል ይሆናል ፤ ግን እንዴት ከታዋቂዎቹ የኢምፔሪያሊስት አገሮች ውስጥ ካልነበረችውና ልትሆንም ከማትችለው ከሩሲያ ጋር ግንኙነት ሊኖረው ይችላል? ለምንድንስ ነው ሩሲያ የሌኒኒዝም አገር ፤ የወዝአደሩ አብዮት ቲዮሪና ታክቲክ የትውልድ ቦታ የሆነችው?

መልሱ ባጭሩ አንደኛ ሩሲያ እነዚህ ሁሉ የኢምፔሪያሊዝም ቅራኔዎች ያተኮሩባት ኢላማ ነበረች ።

ሁለተኛ ከሌላ ከማንኛውም አገር ይበልጥ ለሬቮሉሽኑ ብቁ የነበረች ፤ ስለዚህም እነዚህን ሁሉ ቅራኔዎች በአብዮታዊ መንገድ ለመፍታት ችሎታ የነበራት እሱዋ ብቻ ስለነበረች ነው ።

እነዚህንም ሁለት ቀደምት ምክንያቶች በዝርዝር ለመረዳት እንዲቻል በቅድሚያ የዛር (ንጉሣዊ) አገዛዝ የሰፈነበት ሩሲያ ሁሉም አይነት ጭቆና ማለትም ካፒታ

ሊስት ፤ ቅኝ ግዛታዊና ወታደራዊ እጅግ በጣም አረመኔዊና ኢሰብአዊ በሆነ መልኩ የሚታይባት ሀገር እንደነበረች መታወስ አለበት ። በሩሲያ ውስጥ የካፒታል ወሰን የሌለው ሀያልነት ከዛሩ (ንጉሣዊ) ጭካኔ የተሞላበት አገዛዝ ጋር መዳቀሉን ፤ ሩሲያዊ ባልሆኑት ብሄረሰቦች ላይ የሩሲያ ብሄረተኝነት መስፋፋቱን ፤ እንደ ቱርክ ፤ ፐርሺያና ቻይና በዛሩ የጦር ኃይል ተይዘው ከፍተኛ ብዝበዛ የተፈፀመባቸው መሆኑን ማንም የሚያውቀው ነው ። በዚህም ምክንያት ሌኒን የዛርን አገዛዝ "የወታደራዊ ፊውዳል ኢምፔሪያሊዝም" ማለቱ ትክክል ነበር ። የዛር አገዛዝ እጅግ አስከፊ የሆኑ የኢምፔሪያሊዝም ባህርይዎች ክምችት ነበር ።

ከዚህ ሌላ በዛር (ንጉሣዊ) አገዛዝ ስር የነበረችው ሩሲያ ለምእራብ ኢምፔሪያሊዝም ታላቅ ደጀን ነበረች ። ይህም መሰረታዊ የሆኑ የሩሲያን ብሄራዊ ኤኮኖሚ የሚቆጣጠረውን የባእድ ካፒታል በነፃ እንዲገባ በመፍቀድዋ ብቻ ሳይሆን ለምእራብ ኢምፔሪያሊስቶች ወታደሮችም ጭምር በማቀበሏም ነበር ። የእንግሊዝንና የፈረንሳይን ካፒታሊስቶች እጅግ ከፍተኛ የሆነ ትርፍ ለማስከበር ሲባል ፲፩ ሚሊዮን የሩሲያ ጦር ሠራዊት አባሎች ለኢምፔሪያሊስቶች ተሰልፈው ደማቸውን አፍስሰዋል ።

በተጨማሪ የዛር አገዛዝ በምስራቅ አውሮፓ የኢምፔሪያሊስቶች ዘበኛ ብቻ ሳይሆን በፓሪስ ፤ በለንደን ፤ በበርሊንና ብራስልስ በሚያገኛቸው ብድሮች ከሩሲያ ሕዝብ በወለድ አማካይነት በብዙ መቶ ሚሊዮን የሚቆጠር ገንዘብ ለመጭመቅ የምእራብ ኢምፔሪያሊዝም ወኪልም ነበር ።



በመጨረሻም ዛሪዝም ቱርክን ፤ ፐርሺያን ፤ ቻይናን. . .ወዘተ. በመቀራመት ረገድ የምእራብ ኢምፔሪያሊዝም እጅግ ታማኝ አጋር ነበር ። በኢምፔሪያሊስት ጦርነት ውስጥ የዛሩ መንግስት የቃል ኪዳን ደጋፊዎች ከሆኑት ኢምፔሪያሊስቶች ጋር በማበር ጦርነቱን እንዳደረገና በዚህም ጦርነት ውስጥ ሩሲያ ዋነኛዋ ተካፋይ እንደነበረች የማያውቅ የለም ።

ለዚህ ነው የዛሩ መንግሥትና የምእራብ ኢምፔሪያሊዝም ጥቅሞች የተሳሰሩት በመጨረሻም በአንድ የኢምፔሪያሊስት የጥቅም ሰንሰለት ውስጥ የተዋሀዱት ።

ታዲያ ምእራብ ኢምፔሪያሊዝም የዛሪስት ቡርዧ ሩሲያን የመሰለ በምስራቅ በኩል ሀይለኛ የሆነ ደጋፊና በሰው ጉልበትም ፤ በጥሬ ሀብትም እጅግ ሰፊ የሆነ የሀብት ክምችት ላለማጣት ስትል ፤ በሚካሄደው አብዮት ላይ የሞትና የሕይወት ትግል ሳታካሂድ ዝም ብላ ትተዋለች? ፍጹም አትተውም ።

ከዚህም የምንረዳው ማንም በዛር አገዛዝ ላይ ክንዱን ለማንሳት የፈለገ የግዴታ እጁን በኢምፔሪያሊዝም ላይ ያነሳል ። ማንም በዛሪዝም ላይ የሚነሳ የግዴታ በኢምፔሪያሊዝም ላይም መነሳት አለበት ። ምክንያቱም ዛሪዝምን አሽቀንጥሮ ለመጣል የሚያቅድ ማንም ሰው ዛሪዝምን ለማሸነፍ ብቻ ሳይሆን ደህና አድርጎ ለመጠራረግ ካሰበ ኢምፔሪያሊዝምንም አሽቀንጥሮ መጣል አለበት ። ስለዚህም በዛር አገዛዝ ላይ የሚደረግ አብዮት ከኢምፔሪያሊዝም ጋር ወደሚደረገው ትግል ፤ ወደ ወዝአደራዊ አብዮት ማለፍ ነበረበት ።

በዚህን ጊዜ በሩሲያ ውስጥ እጅግ ከፍተኛ ሕዝባዊ አብዮት በመነሳሳት ላይ ነበር ። የተመራውም እጅግ አብዮታዊ በሆነው በወዝአደሩ መደብ ሲሆን

እሱም የሩሲያን ገበሬ የመሰለ ታላቅ አጋር ነበረው ። እንዲህ አይነቱ አብዮት መሀል ላይ ሊቆም የማይችል እየተሳካ በሄደም መጠን ወደፊት በመገስገስ በኢምፔ ሪያሊዝም ላይ የአመጽን ሰንደቅ አላማ እንደሚያነሳ ማረጋገጫ ያስፈልገዋል?

ሩሲያ የግዴታ የኢምፔሪያሊዝም ቅራኔዎች ማተ ኮሪያ ኢላማ የሆነቺው ፤ እነዚህ ቅራኔዎች በተለይ አፀ ያፊና ከመጠን በላይ የመሆናቸው ባህርይ የታየበትና የምእራብን ፋናንስ ካፒታል ከምስራቅ ቅኝ ግዛቶች ጋር የምታያይዝ እጅግ ከፍተኛ የምእራብ ኢምፔሪያሊ ዝም ደጋፊ በመሆኗ ብቻ ሳይሆን ፤ ከነዚህ ጋር ግን ተዳምሮ የኢምፔሪያሊዝምን ቅራኔዎች በአብዮታዊ መንገድ ለመፍታት የሚችል እውነተኛ ሀይል የነበረው ሩሲያ ውስጥ ብቻ ስለነበረ ነው ።

ከዚህም የሚከተለው በሩሲያ ውስጥ ያለው አብ ዮት ወዝአደራዊ አብዮት እንጂ ሌላ ሊሆን አለመቻሉ ነው ። ገና ከጅንሱ አለም አቀፋዊ ባህርይ መያዙ ግዴታ ነበር ። ይህም በመሆኑ የአለም ኢምፔሪያሊዝም የቆመ በትን መሰረት ማናጋት ነበረበት ።

በነዚህ ሁኔታዎች ስር የነበሩ የሩሲያ ኮሚኒስቶች ስራቸውን አጥብበው በሩሲያ አብዮት ብሄራዊ ድንበር ክልል ብቻ የተወሰነ እንዲሆን ሊያደርጉት ሁኔታው አይፈቅድላቸውም ነበር ። አልፈው ተርፈው የጊዜውን ሁኔታ መነሻ በማድረግ የሀገር ውስጥም (ከፍተኛ አብዮ ታዊ ቀውስ) ሆኑ ከሀገር ውጪ ያሉት ሁኔታዎች (ጦር ነቱ) ከሩሲያ ድንበር ተሻግረው እንዲሠሩና እንዲያተ ኩሩ አድርጎ ፤ ትግሉን ወደ አለም አቀፍ መድረክ እን ዲያዛውሩ ፤ የኢምፔሪያሊዝምን ነቀርሳ እንዲያጋልጡ ፤ የካፒታሊዝም መውደቅ ግዴታ እንደሆነ እንዲያረጋ



ግጡ ፤ የሶሻል ትምክህተኝነትንና ሶሻል ፓስፊዝምን እንዲደመስሱና በመጨረሻም ካፒታሊዝምን ከሀገራቸው አሽቀንጥረው በመጣል የዓለም ወዝአደሮች ካፒታሊዝ ምን ለመጣል ያለባቸውን ተግባር የቀለለ ለማድረግ ለወዝአደሩ አዲስ የመዋጊያ መሳሪያ ማለትም የወዝ አደሩን አብዮት ቲዮሪና ታክቲክ እንዲያንጹ አስገድዶ አቸዋል ። የሩሲያ ኮሚኒስቶች ከዚህ ሌላ ሊያደርጉ አይ ችሉም ነበር ። ምክንያቱም በዚህ መንገድ ብቻ ነበር ሩሲያን ወደ ቡርዧው ሥርዓት እንደገና ከመመለስ የሚ ጠበቁ አንዳንድ ለውጦች በአለም አቀፍ ሁኔታ ላይ መምጣታቸውን በሙሉ ልብ መጠበቅ የሚቻለው ።

ለዚህ ነው ሩሲያ የሌኒንዝም ሀገር የሆነቺውና የሩሲያ ኮሚኒስቶች መሪ የነበረው ሌኒንም የሌኒንዝም ፈጣሪ የሆነው ።

በሩሲያና በሌኒን መሀከል የነበረው "አጋጣሚ" ከሞላ ጎደል በ፲፱ነኛው ክፍለ ዘመን ፴ኛ ዓመተ ምህ ረት ውስጥ በጀርመንና በማርክስና ኤንግልስ መሀከል የነበረው ዓይነት አጋጣሚ ነበር ። ልክ ሩሲያ በሀያኛው ክፍለ ዘመን መጀመሪያ ላይ እንደነበረቺው ሁሉ ፤ ጀርመንም በዚያን ጊዜ ለቡርዧ አብዮት የበሰለ ደረጃ ላይ ነበረች ። በዚያን ጊዜ ማርክስ በኮሚኒስት ማኒፌስቶ ላይ ሲጽፍ እንዲህ ብሏል ።

"ኮሚኒስቶች አይናቸውን በብዛት ወደ ጀርመን ያዞራሉ ። ምክንያቱም ያቺ ሀገር ከአውሮፓ ስልጣኔ ይበልጥ በተራቀቀ ፤ እንግሊዝ በአስራ ሰባተኛው ክፍለ ዘመን ከነበራት ወዝአደር እጅግ የበለጠ ወዝአደር ባለበት ሁኔታዎች ስር በሚካሄድ ከቡርዧ አብዮት ዋዜማ ላይ ትገኛለች ። ስለሆነም ምናልባት የጀርመኑ

የቡርዧ አብዮት ለሚከተለው ለወዝአደሩ አብዮት መግቢያ ይሆን ይሆናል ።”

በሌላ አነጋገር የአብዮታዊ እንቅስቃሴ ማእከላዊ ስፍራ ወደ ጀርመን እየተለወጠ ነበር ።

ከላይ ከፍ ብሎ በማርክስ የተገለጸው ሁናቴ የሳይንሳዊ ሶሻሊዝም የትውልድ ቦታ ለምን ጀርመን እንደ ሆነችና የጀርመን ወዝአደር መሪዎች የነበሩትም ማርክስና ኤንግልስ ለምን ፈጣሪዎቹ ሊሆኑ እንደበቁ ማረጋገጫ ለመሆኑ ጥርጣሬ ሊኖር አይችልም ።

በሀያኛው ክፍለ ዘመን መጀመሪያ ላይም ከዚህ ከፍ ባለ ሁናቴ ይኸው አይነት ተመሳሳይ አባባል ለሩሲያ መጠቀስ አለበት ። ያኔ ሩሲያ በቡርዧ አብዮት ዋዜማ ላይ ነበረች ። ይህንንም አብዮት ማካሄድ የነበረባት በአውሮፓ ውስጥ ቀደም ብለው የታዩት ሁናቴዎች ይበልጥ በዳበሩበት ጊዜ ሲሆን ይህንንም የመራችው በ፲፰፻፵፰ አመታት ገደማ ጀርመን (እንግሊዝና ፈረንሳይ ይቅሩና) ከነበራት ወዝአደር ይልቅ ይበልጥ የዳበረ ወዝአደር ስለነበራት ነው ። የነበሩትም ማስረጃዎች በሙሉ ይህ አብዮት ለወዝአደሩ አብዮት መቀስቀሻና መግቢያ ሆኖ ማገልገሉ እንደማይቀር በግልጽ ያመለክቱ ነበር ።

የሩሲያ አብዮት የመጀመሩ ዋዜማ በታየበት በ፲፱፻፩፪ ዓ. ም. ሌኒን ምን መደረግ አለበት? በተሰኘው መጽሐፉ ያሰፈራቸውን የሚከተሉትን ትንቢታዊ ቃላት እንዲሁ እንደአጋጣሚ የተገኙ አድርገን ማየት አንችልም ።



“ታሪክ የማንንም አገር ወዝአደር ከሚገጥሙት ከሁሉም አጣዳፊ ተግባሮች ሁሉ እጅግ አብዮታዊ በሆነው አጣዳፊ ተግባር አሁን እኛን (ማለትም የሩሲያን ማርክሲስቶች) ገጥሞናል ።

“. . .የአውሮፓ አድሀሪነት ብቻ ሳይሆን ፤ ዛሬ ሊጠቀስ የሚችለውንም የኢስያንም አድሀሪነት ጭምር የመደምሰስ ተግባር የሩሲያን ወዝአደር የአለም አቀፍ አብዮታዊ ወዝአደር መሪ ያደርገዋል ።”

በሌላ አነጋገር የአብዮታዊው እንቅስቃሴ ማእከላዊ ስፍራ ወደ ሩሲያ መዛወሩ የማይቀር ነበር ።

እንደምናውቀው በሩሲያ ውስጥ ያለው አብዮት የሚጓዝበት መንገድ የሌኒንን ትንቢት ትክክለኛነት በደንብ አረጋግጦታል ።

እንግዲህ ከዚህ ሁሉ በኋላ እንዲህ አይነት አብዮት የፈጸመችና እንደዚህ አይነት ወዝአደር ያላት አገር የወዝአደሩ አብዮት ቲዮሪና ታክቲክ ትውልድ ቦታ መሆንዋ አያስገርምም ።

የሩሲያ ወዝአደር መሪ የነበረው ሌኒንም ለዚህ ቲዮሪና ታክቲክ ፈጣሪና የአለም አቀፍ ወዝአደሮች መሪ ሊሆን መቻሉ አያስገርምም ።

## ፪. የሌኒንዝም ዘዴ

ቀደም ብዬ ማርክስና ኤንግልስ ባንድ በኩል ሌኒን በሌላ ሆነው በመሀከላቸው በነበረው ዘመን ሁለተኛው ኢንተርናሽናል የበላይ የነበረበት ጊዜ እንደነበር ገልጫለሁ ። ነገሩን ይበልጥ ለማስተካከል በሃሳቢ ያለው የአድር ባይነት በላይነት የይስሙላ (ፎርማል) ሳይሆን በእር

ግጥ ይታይ የነበረውን የበላይነታቸውን ነው ። ለይስሙላ ያህል ሁለተኛው ኢንተርናሽናል ይመራ የነበረው "ታማኝ" ማርክሳዊ በነበረው "በኦርቶዶክሱ" ካውቲስኪይና በሌሎችም ነበር ። ይሁን እንጂ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ግብር የአድርባይነትን መስመር የተከተለ ነበር ። አድርባዮች ከንውስ ከበርቴ ባሕሪያቸው የተነሳ መስሎ ለማደር ሲሉ ከቡርዧው ተዋሀዱ ። በሌላ በኩል "ኦርቶዶክሶቹ" ደግሞ "በፓርቲው ውስጥ ሰላም እንዲኖር" በማለት ከአድርባዮቹ ጋር "አንድነትን ለመጠበቅ" ራሳቸውን ከእነሱ ጋር አግባቡ ። በዚህም የቡርዧው መመሪያና የኦርቶዶክሶቹ መመሪያ ተዘጋ ። ከዚህም የተነሳ አድርባይነት የበላይነቱን ያዘ ።

ይህም ከጦርነቱ በፊት የነበረው ጊዜ ከሌላው ጋር ሲነፃፀር ካፒታሊዝም ሰላማዊ እድገት ያደረገበት ፤ የኢምፔሪያሊዝምን ውድቀት የሚያስከትሉ ቅራኔዎች ገና ይህን ያህል ጎልተው ያልታዩበት ፤ ሰራተኞች ለኢኮኖሚ ጥቅም ሲሉ የሚያደርጉት የስራ ማቆም አድማና የሙያ ማህበሮች ከሞላጎደል "በቅጡ" ማደግ የያዙበት ፤ የምርጫ ውድድሮችና የፓርላማዊ ቡድኖች "አስገራሚ" ውጤት ያስገኙበት ፤ ሕጋዊ የሆኑ የትግል ዘዴዎች ያለቅጥ የሚሞገሱበት ፤ ካፒታሊዝምን ሕጋዊ በሆነ መንገድ "ማጥፋት" ይቻላል ተብሎ የሚታሰብበት ፤ ባጭሩ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች ፋፍተው ስለአብዮቱ ፤ ስለወዝአደሩ የበላይ ገዢነትና ስለ ሰፊው ሕዝብ አብዮታዊ ትምህርት በጥሞና ለማሰብ ምንም ዝንባሌ ያልነበራቸው ጊዜ ነበር ።

ሁለተኛው ኢንተርናሽናል ከተሟላ አብዮታዊ ቲዮሪ ይልቅ ከሰፊው ሕዝብ አብዮታዊ ትግል የተገነጠሉና ወደ አሮጌ ቀኖና የተለወጡ እርስ በርስ የሚቃረኑ



የቲዮሪ መሠረታዊ መንደርደሪያዎችና የቲዮሪ ብጥስጣሾች ነበሩት ። መስሎ ለመቅረብ ያህል የማርክስን ቲዮሪ ይጠቅሳል ፤ ግን ነዋሪና አብዮታዊ የሆነ መንፈሱን ለማጥፋት ብቻ ነበር ።

ከአብዮታዊ መመሪያ ይልቅ ልፍስፍስ የሆነ መደዶና የማይረባ የፖለቲካ ግብይት ፤ ፓርላማዊ ዲፕሎማሲና ፓርላማዊ ሴራ (ስኪሚንግ) ነበረው ። መስሎ ለመቅረብ ያህል "አብዮታዊ" ውሳኔዎችና መፈክሮች ወጥተዋል ። ግን ተቀብረው ለመቅረት ያህል ብቻ ነበር ።

ፓርቲው በራሱ ስህተቶች ላይ ተመስርቶ ትክክለኛ አብዮታዊ ታክቲኮችን እንዳይማርና እንዳይሰለጥን ሊያገንፍሉ የሚችሉ ጥያቄዎች ሆን ተብሎ ላይ ላያቸውን በመጋለብ ወይንም በመሸፋፈን ገሸሽ ይደረጉ ነበር ። መስሎ ለመቅረብ ያህል ግን ሊያገንፍሉ ስለሚችሉ ጥያቄዎች ለመናገር ምንም ቅዋሜ አልነበረም ። ዞሮ ዞሮ ግን አንድ ዓይነት "ተለጣጭ" (ኢላቲክስ) ውሳኔ ላይ ለመድረስ ብቻ ነበር ።

የሁለተኛው ኢንተርናሽናል የአሰራር ዘዴ ጥርቅም ጠቅላላ መልኩና ሁኔታው እንዲህ ነበር ።

ይህ ሁኔታ በእንዲህ እንዳለ የኢምፔሪያሊስት ጦርነቶችና የወዝአደሩ አብዮታዊ ውጊያዎች ጊዜ እየተቃረበ ነበር ። የድሮው አይነት የትግል ዘዴዎች በፊናንስ ካፒታል ወሰን የለሽ ሀያልነት ፊት ብቃት የሌላቸውና ፍሬቢስ መሆናቸው በግልጽ እየተረጋገጠ ነበር ።

በዚህ ሁሉ የተዳመረ ምክንያት የሁለተኛውን ኢንተርናሽናል ጠቅላላ ድርጊት ፤ የአሰራር ዘዴውን በታትኖና ተንትኖ በመመርመር መደዶ አስተሳሰብን ፤

ጠባብ አስተያየትን ፤ የፖለቲካ ሴራን ፤ ከሀዲ ድርጊቶችን ፤ ሶሻል ትምክህተኝነትን ፤ ሶሻል ፓሲፊዝምን መንቅሎ ማውጣት አስፈላጊ ሆነ ። የዛገውንና ጊዜው ያለፈበትን ሁሉ አውጥቶ ለመጣልና አዲስ አይነት መሳሪያዎች ለማነጽ የሁለተኛውን ኢንተርናሽናል ጠቅላላ ጥርቅም መመርመር አስፈላጊ ሆነ ። ይህንን ተቀዳሚ ሴራ ከመፈጸም በፊት በካፒታሊዝም ላይ ጦርነት መጀመር ዋጋቢስ ነበር ። ያለዚህ ስራ ወዝአደሩ በመጪው አብዮታዊ ጦርነቶች ያለበቂ ትጥቅ እንዲያውም ያለምንም ትጥቅ የመቅረት አደጋ ሊያጋጥመው ይችል ነበር ።

የሁለተኛው ኢንተርናሽናልን የበሰበሰና የበከተ በረት የመጥረጉና በጠቅላላ ሁሉንም በታትኖ የመመርመሩ ከቡር ስራ በሌኒንዝም ላይ ወደቀ ።

በእንደዚያ ያለ ሁናቴ ነበር የሌኒንዝም ዘዴዎች የተወለዱትና የታነጹት ።

የዚህ ዘዴ አስፈላጊ ሁኔታዎች ምንድን ናቸው፣ በመጀመሪያ የሁለተኛውን ኢንተርናሽናል የቲዮሪ ቀኖና በሰፊው ሕዝብ የአብዮታዊ ትግል እሳት ውስጥ መፈተን ፤ ይህም ማለት በቲዮሪና በተግባር መሀከል ተበጥሶ የነበረውን አንድነት ወደ ቦታው መመለስ ፤ በሁለቱ መሀከል ያለውን የመለያየት በሽታ እንዲሽር ማድረግ ። ምክንያቱም በዚህ አይነት ብቻ ነው በአብዮታዊ ቲዮሪ የታጠቀ እውነተኛ ወዝአደራዊ ፓርቲ ሊፈጠር የሚቻለው ።

ሁለተኛ ፤ የሁለተኛ ኢንተርናሽናል ፓርቲዎችን መመሪያ በመፈክሮቻቸውና በውሳኔዎቻቸው ሳይሆን (ሊታመን አይቻልምና) በስራቸውና በድርጊታቸው መፈተን ። በዚህ አይነት መንገድ ብቻ ነው የሰፊው ወዝአደር እምነት ሊገኝ የሚቻለውና መገኘትም ያለበት ።

ሶስተኛ ፤ ሰፊውን ሕዝብ ለአብዮታዊ ትግል ለማሰልጠንና ለማዘጋጀት ጠቅላላውን የፓርቲ ስራ በአዲስ አብዮታዊ መስመር ላይ መልሶ ማደርጀት ። ሰፊው ሕዝብ ለወዝአደሩ አብዮት ሊዘጋጅ የሚችለው በዚህ መንገድ ብቻ ነውና ።

አራተኛ ፤ በወዝአደሩ ውስጥ ግለሂስ እንዲኖርና አባሎች በራሳቸው ስህተቶች ላይ ተመስርተው ራሳቸውን እንዲያስተምሩና እንዲያሰለጥኑ ማድረግ ። ሀቀኛ ካድሬዎችና ሀቀኛ የፓርቲው መሪዎች ሊሰለጥኑ የሚችሉት በዚህ አይነት መንገድ ብቻ ነው ።

የሌኒንዝም ዘዴ መሰረቱና ፍሬ ነገሩ እንዲህ ነበር ። ይህ ዘዴ በተግባር ላይ እንዴት ነበር የዋለው፣

የሁለተኛው ኢንተርናሽናል አድርባዮች እንደ ቋሚ ነጥባቸው አድርገው ሁልጊዜ የሚመለሱባቸው በዛ ያሉ ቲዮሪያዊ ቀኖናዎች አሉዋቸው ። እስቲ ጥቂቶቹን እንይ ።

የመጀመሪያው ቀኖና ፤ ወዝአደሩ ስልጣን የሚይዝበትን ሁኔታዎች የሚመለከት ነው ። አድርባዮቹ በአንድ ሀገር ውስጥ ካሉት ሕዝቦች ወዝአደሩ ብዛት ከሌለው ስልጣን ሊወስድ አይገባውም ፡ አይችልምም ይላሉ ። በቲዮሪም ሆነ በተግባር ይህንን የቂል ንድፈ ሃሳብ (ቲሲስ) የሚደግፍ አንዳችም ነገር ስለሌለ ምንም ማረጋገጫ አልሰጡም ። ይህ ትክክል ነው ብለን እንኳ ብንወስድ ይላል ሌኒን ለሁለተኛው ኢንተርናሽናል ሰዎች ፤ እሺ ፤ ለምሳሌ የሕዝቡ አነስተኛ ክፍል የሆነው ወዝአደር ብዙሀኑን ሰርቶአደር ሕዝብ ከራሱ

ጋር ለማሰለፍ የሚችልበት ታሪካዊ ሁናቴዎች (ጦርነት ፣
የገጠር ቀውስ. . .ወዘተ.) ተነሳ እንበል ። ያኔ ለምን
ስልጣን አይወስድም? ለምንድን ነው ወዝአደሩ በአለም
አቀፍና በሀገር ውስጥ አመቺ ሁኔታዎች እየተጠቀመ
የካፒታሊዝምን ግንባር ሸንቁሮ የመጨረሻ መፍትሄ የሚ
መጣበትን ጊዜ የማያፋጥነው? በ፲፱ኛው ምእተ ዓመት
አጋማሽ ላይ ማርክስ በጀርመን ውስጥ የወዝአደሩ አብ
ዮት "በዳግመኛ የገበሬ ጦርነት" ሊደገፍ ቢቻል ኖሮ
"እጅግ ግሩም" ይሆን ነበር አላለም? በዚያን ጊዜ
በጀርመን ውስጥ የነበሩ ወዝአደሮች ቁጥር ለምሳሌ
ሩሲያ በ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ከነበራት ጋር ሲነፃፀር
አነስተኛ እንደነበር የታወቀ ነገር አይደለም? የሩሲያ
ወዝአደራዊ አብዮት ተግባራዊ ልምድ የእነዚህ የሁለተ
ኛው ኢንተርናሽናል 'ጀግኖች' ተወዳጅ ቀኖና ፍሬ
እንደሌለውና ባዶ እንደሆነ አላሳየም? የሰፊው ሕዝብ
አብዮታዊ ትግል ተግባራዊ ልምድ ይህንን ጊዜው
ያለፈበት ቀኖና እንደሚያስተባብልና እንደሚደመስስ
ግልጽ አይደለም?

ሁለተኛው ቀኖና ፤ የሀገሪቱን አስተዳደር ሊያደራጁ
የሚችሉ በቂ የሆኑ የሰለጠኑ የባህልና የአስተዳደር ካድ
ሬዎች ከሌሉ ወዝአደሩ ስልጣኑን ይዞ ለመቆየት አይች
ልም ። እነዚህ ካድሬዎች መጀመሪያ በካፒታሊስት
ሥርዐት ውስጥ መሰልጠን አለባቸው ፤ ያኔ ብቻ ነው
ስልጣን ሊወሰድ የሚቻለው የሚለው ነው ። ይህንንም
ልክ ነው ብለን እንውሰድ ይላል ሌኒን ። ግን እንደዚህ
ብናየውስ? መጀመሪያ ስልጣን ጨብጦ ለወዝአደሩ
መዳበር አመቺ ሁናቴዎችን መፍጠር ፤ ከዚያም የሰርቶ
አደሩን ሰፊ ህዝብ የባህል ደረጃ ከፍ ለማድረግ እጅግ
ከፍተኛ እርምጃ በመውሰድ ከሰራተኛው መሀከል እጅግ
ብዙ የሆኑ መሪዎችና አስተዳዳሪዎች የሚሆኑ ካድሬዎ



ችን ማሰልጠን ። የሩሲያው ልምድ ከሰራተኛው ውስጥ
የሚመለመሉት የመሪ ካድሬዎች ከካፒታል ሥርዓት
ስር ይልቅ በወዝአደሩ ሥርዓት ስር መቶ እጅ በተፋ
ጠነ ጊዜ ተገቢውን ሁሉ አሟልተው እንደሚያድጉ
አሳይቶ የለ? የሰፊው ሕዝብ አብዮታዊ ትግል ተግባራዊ
ልምድ ይህኛውንም የአድርባዮች ቲዮራዊ ቀኖና ያለ
አንዳች ርህራሄ እንደሚደመስሰው ግልጽ አይደለም?

ሶስተኛ ቀኖና ፤ ወዝአደሩ ፖለቲካዊ አጠቃላይ
የስራ ማቆም አድማ ዘዴ ሊቀበል አይችልም ፤ ምክን
ያቱም በቲዮሪ በኩል ስህተተኛ ሲሆን (የኤንግልስን
ሂስ ይመልከቱ) በተግባር ደግሞ አደገኛ ነው ። (በሀገ
ሪቱ ውስጥ የተለመደውን የኢኮኖሚ ኑሮ መንገድ
ከማናጋቱም በላይ የሙያ ማህበሮችን ገንዘብ ይጨር
ሳል) ። ለወዝአደሩ የመደብ ትግል ዋነኛ የትግል አይ
ነት ለሆነው ለፓርላማዊ አይነት የትግል ዘዴዎች ምትክ
ሆኖ ሊያገለግል አይችልም ። በጣም ጥሩ ይላሉ
ሌኒንስቶች ። ግን በመጀመሪያ ነገር ኤንግልስ ሁሉንም
አይነት ጠቅላላ የስራ ማቆም አድማ አልነቀፈም ።
እሱ የነቀፈው በወዝአደሩ ፖለቲካዊ ትግል ፈንታ
አናርኪስቶች የሚለፍፉትን ኢኮኖሚያዊ ጠቅላላ የስራ
ማቆም አድማ ብቻ ነው ። ይህን ከፖለቲካዊ ጠቅላላ
የስራ ማቆም አድማ ዘዴ ጋር ምን አገናኘው? ሁለተኛ
ነገር ደግሞ የትስ ቦታና በማንስ ነው ፓርላማዊ አይ
ነት የትግል ዘዴ የወዝአደሩ ዋነኛ የትግል ዘዴ መሆኑ
ተረጋግጦ የሚያውቀው? የአብዮታዊ እንቅስቃሴዎች
ታሪክ ፓርላማዊ ትግል ከፓርላማዊ ትግል ውጪ የሆ
ነውን የወዝአደሩን ትግል ለማደራጀት ደጋፊ ብቻ
መሆኑን ፤ በካፒታሊዝም ስር የሠራተኛው መደብ
እንቅስቃሴ መሠረታዊ ችግሮች የሚፈቱት በሀይል ፤

በሰፊው ወዝአደር ቀጥተኛ ትግል ፤ በጠቅላላ የስራ
ማቆም አድማና በአመጽ መሆኑን አያሳይም? ሶስተኛ ፤
ፖለቲካዊ ጠቅላላ የስራ ማቆም አድማ ዘዴ ለፓርላማዊ
ትግል ምትክ ይሁን ብሎ ሃሳብ ያቀረበው ማነው እሱ?
የትስና መቼስ ነው የፖለቲካዊ ጠቅላላ የስራ ማቆም
ዘዴ ደጋፊዎች ከፓርላማዊ ትግል ውጪ የሆነውን
የትግል አይነት በፓርላማዊ የትግል ዘዴ ለመተካት
የፈለጉት? አራተኛ ፤ በሩሲያ ውስጥ የተካሄደው አብዮት
ፖለቲካዊ ጠቅላላ የስራ ማቆም አድማ ለወዝአደሩ
አብዮት እጅግ ጠቃሚ ትምህርት ቤትና የካፒታሊዝ
ምን ምሽጎች በመውረርያ ዋዜማ ጊዜ ሰፊውን ወዝ
አደር ለማዘጋጀትና ለማደራጀት ምትክ የማይገኝለት
ዘዴ መሆኑን አላሳየም? ታዲያ ለምንድንነው ለተለ
መደው የኢኮኖሚ ኑሮ መረበሽና ለሙያ ድርጅቶች
ገንዘብ ማለቅ ይህ መደዴ የሆነ ሮሮ የአብዮታዊ ትግል
ተግባራዊ ልምድ ይህንንም የአድርባዮች ቀኖና እንደ
ሚደመሰስ ግልጽ አይደለም?

እያለ ይቀጥላል . . .

ለዚህ ነው ሌኒን "አብዮታዊ ቲዮሪ ቀኖና አይደ
ለም ፤ የመጨረሻ መልኩን የሚያገኘውም በእርግጥ
የሰፊው ህዝብና በእርግጥም አብዮታዊ ከሆነ እንቅስ
ቃሴ ጋር በቅርብ ሲገናኝ ብቻ ነው" ያለው ። (ግራ
ክንፍ ኮሚኒዝም) ምክንያቱም ቲዮሪ ተግባርን ማገል
ገል አለበት ፤ ምክንያቱም "ቲዮሪ በተግባር የተነሱትን
ጥያቄዎች መመለስ አለበት" ("የሕዝቡ ወዳጆች"
ምን እንደሆኑ) ምክንያቱም ቲዮሪ በተግባራዊ ውጤቶች
መፈተን አለበት ።

የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች ይጠቀሙ
ባቸው የነበሩትን የተዋቡ አብዮታዊ የፖለቲካ መፈክ



ሮችንና ውሳኔዎችን አንስተን ብንመለከት ፀረ አብዮ
ታዊ ድርጊትን ለመሸፈን የሚደረግን መፍጨርጨር
ማጋለጥ ያስችለናል ። የእነዚህ ፓርቲዎች የፖለቲካ
ተግባሮች ምን ያህል ፍጹም ውሸትና ፍጹም የበሰበሱ
መሆናቸውን ለመገንዘብ "በጦርነት ላይ ጦርነት"
ስለሚለው መፈክር ታሪክን መመልከቱ ብቻ በቂ ነው ።
ሁለተኛው ኢንተርናሽናል በባስል ጉባኤ ወቅት ባደረ
ገው ጉረኛ ሰላማዊ ሰልፍ ኢምፔሪያሊስቶች ጦርነት
ለማንሳት ከደፈሩ አመፅ ሊያስከትል በሚችለው አሰ
ቃቂ ነገር ሁሉና አስፈሪ በሆነው "በጦርነት ላይ ጦር
ነት" በሚለው መፈክር ዙሪያ ወዝአደሩን መደብ
በመሰብሰብ በኢምፔሪያሊስቶች ላይ ለመዝመት
ዝተው ነበር ። በጦርነቱ ዋዜማ ግን የባስልን ውሳኔ
ቀብረው "ለካፒታሊስት እናት ሀገርህ ክብር ስትል
እርስ በርስህ ተጨራረስ" የሚል መፈክራቸውን ለሠ
ራተኛው ደርድረውለታል ። አብዮታዊ መፈክሮችና
አብዮታዊ ውሳኔዎች በተግባር ካልተደገፉ በስተቀር
ሳንቲም እንደማያወጡ ግልጽ አይደለም? የዛሬው የኢ
ምፔሪያሊስት ጦርነት ወደ እርስ በርስ የመደብ ጦር
ነት (ሲቪል ዋር) እንዲለወጥ ሌኒንስቶች ያወጡት
መመሪያ የአድርባይ ፖለቲካዎችን ፍጹም ሀፍረትና
ወራዳነት አጋልጦ የሌኒንዝምን ዘዴ ሙሉ ግርማ በገ
ሀድ አሳይቷል ።

ፓርቲዎችን በወረቀት መፈክራቸውና በመዛግብ
ታቸው እንጂ በድርጊታቸው አንፈርድባቸውም የሚል
የካውትስኪን አድርባይ ጉራ ሌኒን የወዝአደሩ አብ
ዮትና ከሀዲው ካውትስኪ በተሰኘው መጽሐፉ ፤

"መፈክሮችን ማቅረብ ሁኔታውን ይለው
ጣል . . . ብሎ በማሰብ ካውትስኪ ልክ

የንዑስ ከበርቴውን መደዴ መመሪያ ይከተላል ። የቡርዧ ዲሞክራትስ ጠቅላላ ታሪክ ይህንን መሰረተቢስ እምነት ያስተባብለዋል ። ሕዝቡን ለማታለል ሲሉ ቁም ነገሩ ግን ሀቀኛነታቸውን መፈተን ፤ የሚናገሩትን ከሚሰሩት ጋር ማመዛዘንና ሃሳባዊና አወናባጅ በሆኑ ሐረጐች በመርካት ፈንታ ስራዬ ብሎ የመደብ እውነቷን (ሪያሊቲ) መመልከት ነው ።" (ሌኒን ቅጽ ፴፫ ገጽ ፫፻፵፯ ይመልከቱ)

የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች ስለ ግለሂስ የነበራቸውን ፍርሀት ፤ ስህተትን የመሸፋፈን ልምድ ፤ ቁጣን ለመቀስቀስ የሚችሉ ጥያቄዎችን ለማግለል ሲሉ የሚያደርጉትን ድብብቆሽና ፓርቲው ከራሱ ስህተት አብዮታዊ ትምህርቶችን እንዳይቀስም የሚያደርጉትን ጠማማ ሥራቸውን ሁሉ ሌኒን ያለማወላወል አጋልጦታል ። ሌኒን ግራ ክንፍ ኮሚኒዝም በተሰኘው መጽሀፉ በወዝአደሩ ፓርቲ ውስጥ ሊኖር ስለሚገባው ግለሂስ እንዲህ ይላል ፤

"አንድ ፖለቲካ ፓርቲ የራሱን ስህተቶች በሚመለከተው በኩል ያለው ዝንባሌ ፓርቲው ምን ያህል ሀቀኛና ምን ያህልስ ለመደቡና ለሰፊው ሰርቶ አደር ሕዝብ ያለበትን ግዴታ በተግባር እንደሚያሟላ ለመፍረድ ያስችላል ። ይህም ዘዴ እጅግ ጠቃሚና እርግጠኛ ለመሆን ከሚያስችሉ መንገዶች አንዱ ነው ። ስህተቱን አምኖ መቀበል ፤ ለስህተቱ ምክንያት የነበሩትን መርምሮ ማወቅ ፤ ለዚህ ስህተት መነሻ የሆኑትን ሁኔታዎች መተን



ተን ፤ ስህተቱንም ለማረም በሰፊው መወያየት የእውነተኛ ፓርቲ አይነተኛ መለያው ነው ። ፓርቲው ተግባሮቹን የሚያከናውንበት መንገድ ፤ መደቡንና ከዚያም ሰፊውን ሕዝብ የሚያስተምርም መንገድ ይህ ነው ። (ቅጽ ፳፭ ፣ ገጽ ፪፻ ይመልከቱ ።)

አንዳንድ ሰዎች ፓርቲው የራሱን ስህተቶች እያጋለጠ በራሱ ላይ ወቀሳን ማዝነሙ አደገኛ ነው ፤ ምክንያቱም ጠላት በወዝአደሩ ፓርቲ ላይ ላለው ቅዋሜ ሊጠቀምባቸው ይችላል ይላሉ ። ሌኒን እንደዚህ አይነቱን አስተሳሰብ ተልካሻና ፍጹም ስህተተኛ መሆኑን ገና ያኔ በ፲፱፻፬ ዓ. ም. ፓርቲያችን ትንሽና ደካማ በነበረበት ጊዜ አንድ እርምጃ ወደፊት በተሰኘው መጽሐፉ ላይ የጻፈው ይኸውና ።

"ተቃዋሚዎቻችን በኛ አለመግባባትና የእርስ በርስ ክርክር ይቋምጣሉ ፤ ያሽሟጥጣሉ ። በፓርቲያችን ውስጥ ስላሉት ጉድለቶችና ያልተሟሉ ነገሮች አንዳንድ ቁንጽል ጽሁፎችን አውጥተው ለራሳቸው ጥቅም ለማዋል እንደሚጥሩም አይጠረጠርም ። የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቶች በትግሉ ከአሁኑ ደህና አድርገው የጠነከሩ ስለሆነ በእንዲህ አይነቱ ቀላል ነገር ሳይረበሹ ራሳቸውን መውቀሱንና የራሳቸውን ጉድለቶች ያለአንዳች ርህራሄ ማጋለጡን መቀጠል አለባቸው ። እነዚህ ጉድለቶችም የሠራተኛው መደብ እንቅስቃሴ እያደገ ሲሄድ ያለጥርጥር የግዴታ እየተወገዱ ይሄዳሉ ።". (ቅጽ ፯ ፣ ገጽ ፩፻፳፩ ይመልከቱ።)

ባጠቃላይ የሌኒንዝም ዘዴ መለያ ባህርይዎቹ እነዚህ ናቸው ። በሌኒንዝም ትምህርቶች ውስጥ ያሉት ዘዴዎች አብዛኛዎቹ አስቀድሞውኑ በማርክስ ትምህርቶች ውስጥ የነበሩ ናቸው ። በራሱ በማርክስ አባባልም የማርክሲዝም ትምህርቶች በመሰረቱ ተቺና (ክሪቲካል) አብዮታዊ ናቸው ። ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ ድረስ ያለውን የሌኒንን ዘዴ የሚያጥለቀልቀውም ይኸው ተቺና አብዮታዊ የሆነ መንፈስ ነው ። ይሁንናም የሌኒን ዘዴ የማርክስን ዘዴ ወደቦታው መመለስ ብቻ ነበር ብሎ ማሰብ ስህተት ይሆናል ። እንደ እውነቱ ከሆነ የሌኒን ዘዴ የማርክስን ዘዴ እቦታው መመለስ ብቻ ሳይሆን የማርክስን ተቺና አብዮታዊ ዘዴ እንዲሁም የማርክስን ማቴሪያሊስት ዲያሌክቲክስ በይበልጥ ማዳበርና ተጨባጭ ማድረግ ነው ።

## ፫. የሌኒንዝም ቲዮሪ

ከዚህ ዋና ሀሳብ ሶስት አርእስቶች እወስዳለሁ ።

ሀ. ለወዝአደሩ እንቅስቃሴ የቲዮሪ አስፈላጊነት ።

ለ. የግብታዊ (ስፖንቴንቲ) ‘ቲዮሪ’ ሂስ ።

ሐ. የወዝአደሩ አብዮት ቲዮሪ ።

፩. የቲዮሪ አስፈላጊነት (ጠቃሚነት) አንዳንዶች ሌኒንዝም ማርክሳዊ ንድፈ ሃሳብን በተግባር መተርጎም ዋነኛው ሙያው ስለሆነ ስለቲዮሪ ደንታም የለው ፤ ስለዚህም ከቲዮሪ ይልቅ ለተግባር ቅድሚያ ይሰጣል ይላሉ ። ፕሌክሀኖቭ ሌኒን ለቲዮሪ በተለይም ለፍልስፍና “እንደማይጨነቅ” አድርጎ ደግሞ ደጋግሞ አሹፎበታል ። ዛሬም በብዙዎቹ ሌኒንስት በሆኑ ተግባራዊ ታጋዮች ዘንድ ፤ በተለይም ጊዜው ከጣለባ



ቸው እጅግ ብዙ የሆነ ተግባራዊ ስራ የተነሳ ቲዮሪ እስከዚህም ትልቅ ስፍራ እንዳልሰጡት የታወቀ ነው ። ይህ ከላይ የተደረደረው ጉዳይ ግን በጣም እንግዳ የሆነ በሌኒንና በሌኒንዝም አስተሳሰብ ፍጹም ስህተትና በምንም አይነት ከእውነተኛው ነገር ጋር ግንኙነት የሌለው ፤ ተግባራዊ ታጋዮች ቲዮሪን ወደጎን ገሸሽ ለማድረግ የሚያደርጉትም ሙከራ ከጠቅላላው የሌኒንስት መንፈስ ጋር የሚቃረንና ለሥራቸውም ከፍተኛ አደጋን የሚያስከትል መሆኑን መግለጽ አለብኝ ።

ቲዮሪ በልዩ ልዩ አገሮች ውስጥ የተካሄዱ የሰራተኛው መደብ እንቅስቃሴዎች አጠቃላይ ልምድ ነው ። የአብዮታዊ ተግባር መጓዣ መንገድ የአብዮታዊ ቲዮሪ ብርሃን ካልፈነጠቀበት በጨለማ ውስጥ እንደ መደናበር ያህል ነው ። ቲዮሪም ከአብዮታዊ ተግባር ጋር ካልተያያዘ ዋጋቢስ ነው ። በሰራተኛው መደብ እንቅስቃሴ ውስጥ ቲዮሪ ከአብዮታዊ ተግባር ጋር ፍጹም በማይለያዩ ግንኙነት ላይ ከተገነባ እጅግ ታላቅ ሀይል ሊሆን ይችላል ። ምክንያቱም የወዝአደሩ እንቅስቃሴ በራሱ እንዲተማመን የሚያደርገው ፤ ትክክለኛውን አቅጣጫ የማመላከት ሀይል ያለው ፤ በአካባቢው ስላሉት ድርጊቶች ውስጣዊ ግንኙነቶች ሊያስረዳው የሚችለው አብዮታዊ ቲዮሪ ብቻ በመሆኑ ነው ። አንድ አብዮታዊ ሂደት በሚያልፍባቸው ደረጃዎች የጊዜውን ሁኔታ መርምሮ የመደቦችን አሰላለፍ ጉዞ መተለም ብቻ ሳይሆን ወደፊትም እንዴትና በምንስ አቅጣጫ እንደሚጓዝ ተገንዝቦ ለተግባር የሚያዘጋጅ ቲዮሪ ብቻ ነው ። “ያለአብዮታዊ ቲዮሪ አብዮታዊ እንቅስቃሴ ሊኖር አይችልም” ብሎ እጅግ በጣም ታዋቂ የሆነውንና በየጊዜውም ሲጠቀስ የሚኖረውን ቲስስ ያቀረበው ሌኒን ነው ። (ቅጽ ፬ ፡ ገጽ ፫፻፹ ይመልከቱ ።)

የሩሲያ የወዝአደር ፓርቲ በጊዜው የወደቀበትን የዓለም ወዝአደሮችን በቀደምትነት የመምራት ኃላፊነት ስንመለከት ፤ ያለንበትንና ውስብስብ የሆነውን የዓለም አቀፍና የሀገር ውስጥ ሁኔታ ስናስተውል በተለይም እንደኛ ላለው ፓርቲ የቲዮሪን ታላቅነት ከማንም ሰው ይበልጥ የተረዳው ሌኒን ነበር ። ገና ያኔ በ፲፱፻፪ ዓ.ም. የኛን ፓርቲ ልዩ ሚና አስቀድሞ በማየት ፤ የግንባር ቀደም ተዋጊ ሚና ሊሟላ የሚችለው እጅግ በተራቀቀ ቲዮሪ በሚመራ ፓርቲ ብቻ ነው” (ቅጽ ፩ ፡ ገጽ ፫፻፹ ይመልከቱ ።) ብሎ የጠቀሰው ያኔ እንኳን አስፈላጊ ነው ብሎ በማሰቡ ነበር ።

ስለፓርቲያችን ሚና ሌኒን በቅድሚያ የተናገረው በተረጋገጠበት በአሁኑ ወቅት ይህ የሌኒን ንድፈ ሀሳብ (ቲስስ) ሀይለኛና ልዩ ክብደት እንደሚያገኝ እስከ ዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገው ።

ምናልባት ፤ ሌኒን ለቲዮሪ የሰጠውን ከፍተኛ ግምት ሊገልጥልን የሚችለው ከኤንግልስ ጀምሮ እስከ እሱ ጊዜ ድረስ የተገኙትን እጅግ ከፍተኛ የሆኑ የሳይንስ ውጤቶች በማቴሪያሊስት ፍልስፍና መሠረት ላይ ለማጠቃለልና በማርክሲስቶች መሀል የነበረውን ፀረ ማቴሪያሊስት አዝማሚያዎች ሰፋ ባለ ወቀሳ ለመተንተን እጅግ ከባድ የሆነውን ተግባር የፈጸመው ሌላ ሰው ሳይሆን ሌኒን መሆኑ ነው ። ኤንግልስ “ማቴሪያሊዝም ከእያንዳንዱ አዲስ ውጤት ጋር አዲስ መልክ መያዝ አለበት” ያለውን መሪ ሃሳብ ሌኒን ራሱ ለነበረበት ጊዜ ማቴሪያሊዝምና ኢምፔሪዮ ክሪቲሲዝም በተሰኘው ተደናቂ መጽሐፉ የፈጸመው መሆኑ የታወቀ ነው ። ሌኒን ለፍልስፍና “አይጨነቅም” እያለ ማሾፍ



ይወድ የነበረው ፕሊክሀኖቭ እንዲህ አይነቱን ተግባር ለመፈጸም ምንም አይነት ቅን ሙከራ ለማድረግ እንዳልደፈረ ደህና አድርጎ የታወቀ ነው ።

፱. የግብታዊነት “ቲዮሪ” ሂስ ወይንም በእንቅስቃሴው ውስጥ የግምባር ቀደሙ ፓርቲ ሚና ፤ የግብታዊነት “ቲዮሪ” የአድርባይነት ቲዎሪ ነው ። እሱም የሰራተኛ ድርጅቶችን እንቅስቃሴ (ሌበር ሙቭመንት) ግብታዊነት የሚያመልክ ፤ የሰራተኛውን መደብ ግንባር ቀደም የመሪነት ሚና ፤ የሰራተኛውን መደብ ፓርቲ የሚክድ ቲዮሪ ነው ።

ግብታዊነትን የማምለክ ቲዮሪ ያለጥርጥር ከሰራተኛው መደብ እንቅስቃሴ አብዮታዊ ባህርይ ጋር ይቃረናል ። እንቅስቃሴው ከካፒታሊዝም መሰረቶች ጋር የሚደረግን ትግል ይቃወማል ። እንቅስቃሴው “በካፒታሊዝም ዘንድ” መልስ “ሊያገኙ” በሚችሉና “ተቀባይነት” በሚኖራቸው የጥያቄዎች መስመር ብቻ እንዲጓዝ ይደግፋል ። በጠቅላላው “በአነስተኛ ቅዋሜዎች” ላይ የሚያተኩርን የትግል መስመር ይደግፋል ። የግብታዊነት ቲዎሪ የሙያ ድርጅቶች (ትሬድ ዩኒየኒዝም) ርእዮተ አለም ነው ።

ግብታዊነትን የማምለክ ቲዮሪ ለግብታዊው እንቅስቃሴ በፖለቲካ በኩል የነቃና እቅድን የተከተለ ባህርይ መስጠትን ያለጥርጥር ይቃወማል ። ፓርቲው በሰራተኛው መደብ ግንባር ሆኖ መራመዱን ፤ ፓርቲው ሰፊውን ሕዝብ ወደ ፖለቲካ ንቃት ደረጃ ከፍ ማድረጉን ፤ ፓርቲው እንቅስቃሴውን መምራቱን ይቃወማል ። እንቅስቃሴው የራሱን የግል ጎዳና እንዲከተል በእንቅስቃሴው ውስጥ ያሉ በፖለቲካ የነቁ ክፍሎች እንዳይገ

ስጹት ይፈልጋል ። ፓርቲው ከግብታዊው እንቅስቃሴ ጀርባ መጎተቱንና ዝም ብሎ እንቅስቃሴውን በምን ቸገረኝነት እንዲመለከተው ይደግፋል ። የግብታዊነት ቲዮሪ በእንቅስቃሴው ውስጥ የሚገኙትን የነቁ ክፍሎችን የማቃለል ፤ "የጭራነት" (ክህቮስቲዝም) ርእዮተ አለምና የማንኛውም አይነት አድርባይነት ሎጂካዊ መሰረት ነው ።

ገና ከመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት[2] በፊት በአደባባይ የታየው ይህ ቲዮሪ በተግባር በኩል ተከታዮቹ የሆኑትና "ኤኮኖሚስቶች" ተብለው የሚታወቁት ወገኖች በሩሲያ ውስጥ ነፃ የሆነ የሰራተኞች ፓርቲን አስፈላጊነት እንዲክዱ ፤ የሰራተኛው መደብ የዛር አገዛዙን ለመጣል የሚያደርገውን አብዮታዊ ትግል እንዲቃወሙ ፤ በእንቅስቃሴው ውስጥ የሙያ ድርጅት መመሪያን ብቻ እንዲሰብኩ ፤ ባጠቃላይ የሰራተኛው ድርጅቶችን እንቅስቃሴ ለለዘብተኛ ቡርዧው መሪነት አሳልፈው እንዲሰጡ ገፋፍቷቸዋል ።

በድሮው የእስክራ[3] ጋዜጣ አገልግሎት በተካሄደው ትግልና ምን መደረግ አለበት? በሚለው የሌኒን መጽሐፍ የተደረገው "የጭራነትን" ቲዮሪ የማጋለጥ ውብትችት "ኢኮኖሚዝም" የተሰኘውን አድርባይነት ከመደምሰሱም በላይ ለሩሲያ ሰራተኛ መደብ እውነተኛ አብዮታዊ እንቅስቃሴ የቲዮሪ መሰረቶችን ፈጥሯል ።

ያለ እንደዚህ አይነት ትግል በሩሲያ ውስጥ እንኳን ነፃ የሆነ የሰራተኞች ፓርቲ ሊፈጠርና በአብዮቱም ውስጥ የመሪነትን ቦታ ሊይዝ ቀርቶ መታሰቡም እንኳን ፍጹም ዋጋቢስ ይሆን ነበር ።



ግብታዊነትን የማምለክ ቲዮሪ የሩሲያ ብቻ የሆነ ክስተት አይደለም ። በሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች ውስጥ በሙሉ ለየት ባለሁኔታ ያለቅጥ የተስፋፋ ነበር ። እዚህ ላይ በሃሳቤ ያለው በሁለተኛው ኢንተርናሽናል መሪዎች የተዋረደው "የምርት ሀይሎች" ቲዮሪ የተሰኘው ነው ። ይህም ቲዮሪ የማንኛውንም ነገር ትክክለኛነት የሚያሳይና ሁሉንም ሰው የሚያግባባ ፤ ተጨባጭ እውነቶችን (ፋክትስ) መዝግቦ አስቀምጦ ሰዎች ሁሉ ከሰለቻቸውና እጅ እጅ ካላቸው በኋላ የሚያብራራ ፤ ከመዘገባቸው በኋላም ረክቶ ቁጭ የሚል ነው ። ማርክስ ማቴሪያሊስት ቲዮሪ አለምን በማብራራት ብቻ ራሱን መወሰን የለበትም ፤ መለወጥ መቻልም አለበት ብሏል ። ነገር ግን ካዎቲስኪና ጓደኞቹ ለዚህ አልተጨነቁም ። በማርክስ የመጀመሪያው ፎርሙላ ብቻ ረክተው መቀመጥን ይመርጣሉ ።

ይህ "ቲዮሪ" ከተገለፀበት ከብዙዎቹ ምሳሌዎች ውስጥ አንዱ ይኸውና ። ከኢምፔሪያሊስቶች ጦርነት በፊት ኢምፔሪያሊስቶች ጦርነት ከጀመሩ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች "በጦርነት ላይ ጦርነት" እናውጃለን ብለው አስፈራርተው ነበር ተብሏል ። በዚህ ጦርነትም ዋዜማ እነዚህ ፓርቲዎች "በጦርነት ላይ ጦርነት" የሚለውን መፈክር ቀይረው የሱ ተቃራኒ የሆነ በስራ ላይ አውለዋል ። ይህም "ለእናት አገር ጦርነት" የሚል ነበር ። ከዚህ መፈክር መለወጥ የተነሳ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ሰራተኞች ወደሞት ተላኩ ተብሏል ። ሆኖም ለዚህ የሚወቀሱ ሰዎች አሉ ፤ ለሰራተኛው መደብ ታማኝ የነበረ ወይንም የከዳ ሰው ነበር ብሎ ማሰብ ስህተት ነው ። እንዴት ተብሎ ። ሁሉም ነገር የሆነው መሆን እንደሚገባው ነው ። በመጀመሪያ ነገር ሁለተኛው ኢንተርናሽናል "የሰላም መሳሪያ"

እንጂ የጦርነት አይመስልም ። ሁለተኛ ነገር በጊዜው
በነበረው "የምርት ሀይሎች የእድገት ደረጃ" ስናይ
ከዚህ የተለየ ሊሆን አይችልም ነበር ። የሚወቀሱት
"የምርት ኃይሎች" ናቸው እንጂ ሌላ አይሆንም ።
የሚስተር ካዎትስኪ "የምርት ሀይሎች ቲዮሪ"
የሚፈቅድልን ትክክለኛው ማብራሪያ ይህ ነው ።
በዚህ "ቲዮሪ" የማያምን ማንም ሰው ማርክሳዊ አል
ነበረም ። የፓርቲዎችስ ሚና? ለእንቅስቃሴው የሚሰጡ
ትስ ጥቅም? እንደ "የምርት ሀይሎች ደረጃ" አይነት
ባለው ወሳኝ ነገር ላይ ፓርቲው ምን ሊያደርግ ይች
ላል? የሚሉት ጥያቄዎች በነካዎትስኪ አይን ቁም
ነገር የላቸውም ።

ተመሳሳይ የሆኑና በዛ ያሉ ማርክሲዝምን ያሳሳቱ
በትን ምሳሌዎች ለመጥቀስ ይቻላል ።

ይህ ትክክለኛ ያልሆነ ፤ የአድርባይነትን እርቃን
ለመሸፈን የታቀደ "ማርክሲዝም" ገና ከመጀመሪያው
የሩሲያ አብዮት በፊት ሌኒን ይዋጋው የነበረው የአው
ሮፓው "ጭራነት" ቲዮሪ አይነት ለመሆኑ እስከዚ
ህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ።

በምእራብ አገሮች ለሚቋቋሙ እውነተኛ አብዮ
ታዊ ፓርቲዎች የዚህ የተሳሳተ ቲዮሪ መደምሰስ
ተቀዳሚው ሁኔታ ለመሆኑ እስከዚህም ማረጋገጫ
አያስፈልገውም ።

፫. የወዝአደሩ አብዮት ቲዮሪ ፤ የሌኒን የወዝአደሩ
አብዮት ቲዮሪ ከሶስት መሠረታዊ ንድፈ ሃሳቦች (ቲስ
ሶች) ይነሳል ።



የመጀመሪያው ንድፈ ሃሳብ (ቲስስ) ፤ በኢንዱስትሪ
በዳበሩት የካፒታሊስት አገሮች የፊናንስ ካፒታል የበላይ
ነት ፤ ሰነዶች (ስቶክስ ኤንድ ቦንድስ) እንደ ተቀዳሚ
የፊናንስ ካፒታል የየእለቱ ዋና መገልገያዎች መሆን ፤
የኢምፔሪያሊዝም መሰረቶች አንዱ የሆነው ካፒታል ከሀ
ገሩ ወጥቶ ወደ ጥሬ እቃዎች ምንጭ መጓዝ ፤ የፊናንስ
ካፒታል የበላይነት ውጤት የሆነው የጥቂት ባለገንዘ
ቦች አገዛዝ ወሰን የለሽ ሃያልነት ፤ ይህ ሁሉ የሞኖፖል
ካፒታሊዝምን ያለቅጥ መበስበስን ፤ በሌላ ወዝ የመኖር
(ፖራሳይት) ባህርይን ይገልፃል ። የካፒታሊስት ትረስ
ቶችና ሲንዲኬቶች የሚጭኑትን ቀንበር መቶ ጊዜ
የከበደ ያደርገዋል ። የሰራተኛው መደብ በካፒታሊዝም
መሰረቶች ላይ ያለውን ጥላቻና ቁጣ ያብሰዋል ። ሰፊ
ውን ሕዝብም መድህኑ ወደሆነውና አማራጭ ወደሌለው
ወደ ወዝአደራዊ አብዮት ይመራዋል ። (ሌኒን ኢምፔሪ
ያሊዝም ይመልከቱ ።)

ስለዚህ የመጀመሪያው ማጠቃለያ ፤ በካፒታሊስት
ሀገሮች ውስጥ የአብዮታዊ ቀውሶች መባባስና በውስ
ጣዊው የወዝአደሩ ግንባር ሥር "በታላላቅ ከተሞች"
ሊፈነዱ የሚችሉ ክፍሎች ማደግ ነው ።

ሁለተኛው ንድፈ ሃሳብ (ቲስስ) ፤ ወደቅኝ ሀገሮችና
ጥገኛ ሀገሮች የሚደረገው የካፒታል ኤክስፖርት ከፍ
ማለት ፤ ጠቅላላውን አለም እስኪሸፍኑ ድረስ "ተጽእኖ
አካባቢዎችን" ማስፋፋትና ቅኝ ግዛቶች መያዝ ፤ የካፒታሊ
ዝም ወደ አለምአቀፍ ስርአት መለወጥና እፍኝ የማይሞሉ
ጥቂት "የሰለጠኑ" ሀገሮች አብዛኛውን የአለም ሕዝብ
በገንዘብ ባርያ ማድረግና በቅኝ ግዛት መጨቆን ነው ።
ይህ ባንድ በኩል የተለያዩ ብሄራዊ ኢኮኖሚዎችንና

ብሄራዊ ድንበሮችን ለውጦ የአለም ኢኮኖሚ ከሚባል አንድ ሰንሰለት ጋር ያቆራኛቸዋል ። በሌላ በኩል ደግሞ የአለምን ሕዝቦች በሁለት ቡድን ይከፍላቸዋል ። ባንድ በኩል እጅግ ሰፊ የሆኑትን ጥገኛና ቅኝ ግዛቶችን የሚጨቁኑና የሚበዘበዙ እፍኝ የማይሞሉ "የሰለጠኑ" የካፒታሊስት ሀገሮች ፤ በሌላ በኩል ደግሞ ከኢምፔሪያሊስት ቀንበር ለመላቀቅ ሲሉ ለመታገል የተገደዱ እጅግ ብዙ የሆኑትን የቅኝ ግዛቶችንና ጥገኛ ሀገሮችን ። (ኢምፔሪያሊዝምን ይመልከቱ ።)

ስለዚህ ሁለተኛው ማጠቃለያ በቅኝ ግዛት ሀገሮች የአብዮታዊ ቀውስ መባባስና በኢምፔሪያሊዝም ላይ የሚያምጹ ክፍሎች በውጭው ማለትም በቅኝ ግዛት ግንባር ማደግ ነው ።

ሶስተኛው ንድፈ ሃሳብ (ቲስስ) ፤ "የተፅእኖ አካባቢዎችና" የቅኝ ግዛቶች በሞኖፖል መያዝ ፤ የካፒታሊስት ሀገሮች በተለያየ ፍጥነት ማደግና አለምን እንደገና ለመከፋፈል አስቀድመው ቅኝ ግዛቶች በያዙትና እኛም "ድርሻችንን" መያዝ አለብን በሚሉት መሐከል ወደሚደረግ እብደት የተቀላቀለው ትግል ማምራት ፤ የተናጋውን ማዕከላዊ አማዛኝ ነጥብ ፤ (ኢኪዊሊብርየም) እቦታው ለመመለስ አይነተኛው ዘዴ የኢምፔሪያሊስት ጦርነቶች ብቻ መሆን ነው ። ይህ ሁሉ በሶስተኛው ግንባር ማለትም በካፒታሊስት አገሮች መሐከል ባለው ግንባር ትግሉ እንዲባባስ ያደርገዋል ። ይህም ኢምፔሪያሊዝምን ያዳከመውና ሁለቱ ግንባሮች ማለትም የአብዮታዊው ወዝአደር ግንባርና የቅኝ አገሮች ነፃ አውጪ ግንባሮች በኢምፔሪያሊዝም ላይ ያላቸውን ትግል ለማፋፋም ህብረት እንዲያበጁ ሁኔታውን ምቹ ያደርግላቸዋል ። (ኢምፔሪያሊዝምን ይመልከቱ)



ስለዚህም ሶስተኛው ማጠቃለያ ፤ በኢምፔሪያሊዝም ስር ጦርነቶች ሊወገዱ አይችሉም ። በአውሮፓ ውስጥ ያለው ወዝአደራዊ አብዮትና በምስራቅ ያለው የቅኝ ግዛት አብዮት በአለም አቀፍ የኢምፔሪያሊስት ግንባር ላይ አለም አቀፋዊ የአንድነት ግንባር መፍጠራቸውም የግዴታ የማይቀር ነው ።

ሌኒን እነዚህን ሶስት ማጠቃለያዎች "ኢምፔሪያሊዝም የሶሻሊስት አብዮት ዋዜማ ነው ።"[4] ብሎ ያጠቃልላቸዋል ። (ቅጽ ፲፱ ፤ ገጽ ፸፩ ይመልከቱ)

ስለወዝአደሩ አብዮት ጥያቄ ፤ ስለአብዮቱ ባህርይ ፤ መጠኑና ጥልቀቱ ፤ ባጠቃላይ አብዮቱ ስለሚከተለው መንገድ የሚኖረን አቀራረብ ራሱ ከዚሁ ጋር ይለወጣል ።

ድሮ ለወዝአደሩ አብዮት መሳካት በቅድሚያ አስፈላጊ ስለሚሆኑ ነገሮች ትንተና ለማድረግ ሲፈለግ ከእያንዳንዱ ሀገር የኢኮኖሚ ሁኔታ (አቋም) አንፃር ይታይ ነበር ። የዚህ አይነቱ አመለካከት ካሁን ወዲያ በቂ አይደለም ። አሁን ነገሩን መመልከት የሚያስፈልገው ከሁሉም ወይንም ከአብዛኛዎቹ አገሮች የኢኮኖሚ ሁናቴ አንፃር ፤ ከአለም ኢኮኖሚ ሁናቴ አንፃር ነው ። ምክንያቱም በተናጠል ያሉ ሀገሮችና ብሄራዊ ኢኮኖሚዎች ራሳቸውን የሚችሉ ክፍሎች መሆናቸው ቀርቶ የአለም ኢኮኖሚ በሚባል አንድ ሰንሰለት ውስጥ የተቆራኙ ሆነዋል ። ምክንያቱም የድሮው "የተገራ" (ካልቸርድ) ካፒታሊዝም ወደ ኢምፔሪያሊዝም ተለውጧል ። ኢምፔሪያሊዝም ደግሞ የአብዛኛው የአለም ህዝብ እፍኝ በማይሞሉ "የሰለጠኑ" አገሮች በቅኝ ሀገሮች የመጨቆንና በገንዘብ ባርያ የመደረግ አለም አቀፍ ስርአት ነው ።

ድሮ በእያንዳንዱ ሀገር በተለይም በዚህ ወይንም
በዚያ በኢኮኖሚ እድገት በገፋ ሀገር ለወዝአደሩ አብ
ዮት ነባራዊ ሁኔታዎች መኖር አለመኖራቸውን መናገር
ተቀባይነት ነበረው ። ይህ አይነቱ አመለካከት ካሁን
ወዲያ በቂ አይደለም ። አሁን ጠቅላላው የአለም ኢም
ፔሪያሊስት ኢኮኖሚ ስርአት እንደ አንድ ሙሉ አካል
ተወስዶ በዚህ ውስጥ ለአብዮቱ የነባራዊ ሁኔታዎችን
መኖር መናገር አለብን ። በይበልጥም ጠቅላላ ስርአቱ
እንዳለ ከአሁኑ ለአብዮቱ ምቹ ከሆነ ፣ እንዲያውም በይ
በልጥ በትክክል ለመናገር የበሰለ ስለሆነ በዚህ ስር
አት ውስጥ የአንዳንድ በኢንዱስትሪ እምብዛም ያል
ገፉ አገሮች መኖር ለአብዮቱ እንደማይጋፋት ባላጋራ
ሆኖ ሊቆጠር አይችልም ።

ድሮ በዚህ ወይንም በዚያ በኢንዱስትሪ በገፋ
አገር ያለ ወዝአደራዊ አብዮት የተለየና ራሱን እንደ
ቻለ አድርጎ ፣ አንድን የተለየ የካፒታልን ብሄራዊ ድን
በር እንደ ራሱ ተቃራኒ መቃወሙ ተቀባይነት ነበረው ።
ይህ አይነቱ አመለካከት ካሁን ወዲያ በቂ አይደለም ።
አሁን ስለአለም ወዝአደራዊ አብዮት መናገር አለብን ።
ምክንያቱም የተለያዩት የካፒታል ብሄራዊ ግንባሮች
አሁን የአለም ኢምፔሪያሊዝም ግንባር በሚባል አንድ
ሰንሰለት ውስጥ ተቆራኝተዋል ። ይህንንም በሁሉም
አገሮች በሚገኙ አብዮታዊ እንቅስቃሴዎች የጋራ ግን
ባር መቃወም ግዴታ ነው ።

ድሮ የወዝአደሩ አብዮት የአንድ የተወሰነ ሀገር
ውስጣዊ እድገት ውጤት ብቻ ነው ተብሎ ይገመት
ነበር ። ይህ አመለካከት ካሁን ወዲያ በቂ አይደለም ።
አሁን የወዝአደሩ አብዮት በተቀዳሚ በአለም ኢምፔሪ
ያሊስት ስርአት ውስጥ የቅራኔዎች እድገት ውጤት ፣



በአንድ ወይም በሌላው አገር ውስጥ የአለም ኢምፔሪ
ያሊስት ግንባር ሰንሰለት የመበጠስ ውጤት ተደርጎ
መታየት አለበት ።

የት ነው አብዮቱ የሚጀምረው? የትና በየትስ
ሀገር ነው የካፒታል ግንባር (ድንበር) በመጀመሪያ
ሊሸነቆር የሚቻለው?

ኢንዱስትሪዎች በይበልጥ በዳበሩበት ፣ ወዝአደሩ
ከህዝቡ አብዛኛው ክፍል በሆነበት ፣ የበለጠ ባህል ባለ
በት ፣ የበለጠ ዲሞክራሲ ባለበት ፣ ይህ ነበር ድሮ የሚሰ
ጠው መልስ ።

የሌኒኒስት አብዮታዊ ቲዮሪ ይህንን አይቀበልም ።
የግዴታ ኢንዱስትሪ ይበልጥ በዳበረበትና ወዘተ.
አይደለም ይላል ። የካፒታል ግንባር የሚሸነቆረው
የኢምፔሪያሊዝም ሰንሰለት በጣም ደካማ ወይንም
ልል በሆነበት አገር ነው ። ምክንያቱም የወዝአደሩ አብ
ዮት የአለም ኢምፔሪያሊስት ግንባር ሰንሰለት በጣም
ደካማ በሆነበት ቦታ የመበጠሱ ውጤት ነው ። አብዮ
ቱን የጀመረውና የካፒታልን ግንባር የሰነጣጠቀው ሀገር
በካፒታሊስቶች አባባል ‘ከዳበሩና’ በካፒታሊዝም ጠቅ
ላላ መዋቅር ስር ከቀሩ አገሮች ያነሰ እድገት ያለው
ሀገር ሊሆን ይችላል ።

በ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የአለም ኢምፔሪያሊስት ግንባር
ሰንሰለት ከሌሎች ሀገሮች ሁሉ በሩሲያ ውስጥ ደካማ
ነበር ። ሰንሰለቱ የተበጠሰውና ለወዝአደሩ አብዮት
መውጫ ቀዳዳ እንዲኖር ያስቻለውም እዚያ ነበር ።
ለምን? ምክንያቱም በሩሲያ ውስጥ ታላቅ ህዝባዊ
አብዮት በመካሄድ ላይ ነበር ። ግንባር ቀደም ሆኖ የመ
ራውም አብዮታዊው ወዝአደር ሲሆን እሱም በመሬት

ከበርቴዎች ሲጨቁንና ሲበዘብዝ የነበረውን ስፈውን የገበሬ መደብ የመሰለ አጋር ነበረው ። ምክንያቱም እዚያ የነበረው አብዮት ቅዋሜ ይደርስበት የነበረው የዛር አገዛዝ ከመሰለ ምንም አይነት የሞራል ተደማጭነት ካልነበረውና በጠቅላላው ህዝብ ከተጠላ ፣ እጅግ አስጠሊታ ለሆነ ኢምፔሪያሊዝም ወኪል ስለነበር ነው ። ምንም እንኳ ሩሲያ በካፒታሊስቶች አባባል ፣ ለምሳሌ ከፈረንሳይ ወይንም ከጀርመን ፣ ከእንግሊዝ ወይንም ከአሜሪካን ያነሰ ያደገች አገር ብትሆንም ሰንሰለቱ በሩሲያ ውስጥ ይበልጥ ደካማ መሆኑ ተረጋገጠ ።

ወደፊትስ በቅርብ ጊዜ ውስጥ የት ነው ሰንሰለቱ የሚበጠሰው? አሁንም በጣም የላላበት ቦታ ነው ። ለምሳሌ ሰንሰለቱ ህንድ ውስጥ መበጠሱ ሊሆን የማይቻል ነገር አይደለም ። ለምን? ምክንያቱም ያቺ ሀገር ወጣት ፣ ታጋይና አብዮታዊ ወዝአደር አላት ። ወዝአደሩም ብሄራዊ የነፃነት እንቅስቃሴን የመሰለ አጋር ፣ ያለጥርጥር ሀይለኛና ጠቃሚ የሆነ አጋር አለው ። ምክንያቱም እዚያ አብዮቱ የባእድ ኢምፔሪያሊዝምን ከመሰለ ታዋቂ ጠላት ጋር ስለተፋጠጠና ይህም ጠላት ምንም አይነት የሞራል ድጋፍ የሌለው ፣ በመላው የተጨቆነና የተበዘበዘ የህንድ ሰፊ ህዝብ በሚገባ የተጠላ ስለሆነ ነው ።

በጀርመንም እንደዚሁ ሰንሰለቱ ሊበጠስ ይችላል ። ለምን? በህንድ ሀገር ውስጥ በመስራት ላይ ያሉ ሁኔታዎች (ፋክተርስ) በጀርመንም ውስጥ መስራት ጀምረዋል ። ይሁንና በህንድና በጀርመን መሀከል ያለው እጅግ ከፍተኛ የሆነ የእድገት ደረጃ ልዩነት በጀርመን አብዮት እርምጃና ውጤት ላይ ተፅዕኖ ወይንም ምልክት መተዉ አይቀርም ።



ለዚህ ነው ሌኒን እንዲህ ያለው ።

"የምእራብ አውሮፓ ካፒታሊስት አገሮች ወደ ሶሻሊዝም የሚያደርጉትን እድገት የሚያሟሉት. . .ሶሻሊዝም በእነሱ ውስጥ ተስተካክሎ "በመብሰሉ" ሳይሆን አንዳንድ ሀገሮች በሌሎች በመበዝበዛቸው ፣ በኢምፔሪያሊስት ጦርነቶች ውስጥ በመጀመሪያ የሚሸነፉት ሀገሮች መበዝበዝ ከጠቅላላው የምስራቅ መበዝበዝ ጋር በመጣመሩ ነው ። በሌላ በኩል ደግሞ ከመጀመሪያው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት የተነሳ ምስራቅ ያለጥርጥር ወደ አብዮታዊ እንቅስቃሴ መጥቷል ። ያለጥርጥር ወደ አለም አብዮታዊ እንቅስቃሴ አጠቃላይ ማእበል ተጎትቷል ።" (ቅጽ ፳፮ ፣ ገጽ ፩፻፲፫—፩፻፲፮ ይመልከቱ)

በአጭሩ ፣ የኢምፔሪያሊስት ግንባር ሰንሰለት እንደ ሕግ ሆኖ መበጠስ ያለበት ግንኙነቱ በላላበት ቦታ ነው እንጂ የግዴታ ካፒታሊዝም ይበልጥ ባደገበት ፣ ይህን ይህን ያህል እጅ ከመቶ ወዝአደሮች ያሉበት ፣ ይህን ይህን ያህል እጅ ከመቶ ገበሬዎች ያሉበት . . ወዘተ. ቦታ መሆን የለበትም ።

ስለዚህ ነው ስለወዝአደሩ አብዮት ጥያቄ ሲነሳ በሁለተኛው ኢንተርናሽናል ችኩዎች (ዶክትሪነሮች) ያን ያህል ልዩ ግምት የተሰጠው በአንድ አገር ውስጥ ካለው ሕዝብ ከመቶ ይህን ያህል ወዝአደር የሚለው የእስታትስቲክስ ቅምር ዋጋ ቢስ የሚሆነው ። እነዚህ ሰዎች ኢምፔሪያሊዝምን ያልተረዱና አብዮቱን እንደ ተስቦ የሚፈሩ ናቸው ።

ከዚህም በመቀጠል ፣ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ጀግኖች በቡርዧ ዲሞክራቲክ አብዮትና በወዝአደሩ

አብዮት መሀከል ሁለቱን ከሞላ ጎደል በተራዘመ ጊዜ የሚለያያቸው ሽለቆ ወይንም የቻይና ግንብ አለ ይላሉ ። በዚህም ጊዜ ውስጥ ቡርዧው ስልጣን ከያዘ በኋላ ካፒታሊዝምን ያሳድጋል ። ወዝአደሩም ደግሞ በካፒታሊዝም ላይ ለሚደረገው "ወሳኝ ትግል" ራሱን ያዘጋጃል ፤ ጉልበቱን ያጠናክራል ። ይህም ጊዜ በብዙ አመታት ይቆጠራል ይላሉ ። ይህ "የቻይና ግንብ" ቲዮሪ በኢምፔሪያሊዝም ሁኔታዎች ስር ምንም አይነት ሳይንሳዊ ትርጉም እንደሌለውና ለቡርዧው ፀረአብዮታዊ ፍላጎት ከለላና መደበቂያ ሆኖ የሚያገለግል ዘዴ ብቻ እንደሆነና ሊሆንም እንደሚችል እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ። ኢምፔሪያሊዝም በጦርነትና በግጭት ሁኔታዎች ተጠምዶ እያለና "በሶሻሊስት አብዮት ዋዜማም" "ታዳጊው" "ካፒታሊዝም" "የሚያጣጥር" ካፒታሊዝም ሲሆን ፤ በመላው የአለም . ሀገሮች አብዮታዊ እንቅስቃሴዎች እያደጉ ፤ ኢምፔሪያሊዝም ይህ ቀረኝ ሳይል ከሁሉም አድሀሪ ሀይሎች ከዛር አገዛዝና ከገባርነት ስርአት ጋር ራሱን ሲያስተባብርና በዚህም ከምእራብ ወዝአደራዊ እንቅስቃሴ እስከ ምስራቁ የነፃነት እንቅስቃሴ ድረስ የአብዮታዊ ሀይሎችን አንድ መሆን ግዴታ ሲያደርግ ፤ ከኢምፔሪያሊዝም ጋር ትግል ሳይደረግ የፊውዳል አገዛዝ ርዝራዦች ማውደም የማይቻል ነገር ሲሆን ፤ ከሞላ ጎደል በአደገ ሀገር የሚካሄድ የቡርዧ ዲሞክራቲክ አብዮት በእንዲህ አይነቱ ሁኔታ ስር ከወዝአደሩ አብዮት እንደሚጠጋ ፤ የፊተኛው ወደ ኋለኛው እንደሚሸጋገር እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልግም ። በሩሲያ ውስጥ የተካሄደው አብዮት ታሪክ ይህ ቲስስ ትክክለኛና የማያወዛግብ ለመሆኑ ግልፅና ተጨባጭ የሆነ ማረጋገጫ ሰጥቷል ። ሌኒን ገና በ፲፱፻፭ ዓ.ም. በመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት ዋዜማ ጊዜ ሁለት



ታክቲኮች በተሰኘው መጽሐፉ የቡርዧ ዲሞክራቲክ አብዮትና ሶሻሊስት አብዮት በአንድ ሰንሰለት ላይ እንዳሉ ሁለት መገናኛዎች ፤ በሩሲያ አብዮት ጠቅላላ ጉዞ ውስጥ እንደ አንድና ሙሉ የሆነ መልክ አድርጎ የገለፀው ያለምክንያት አልነበረም ።

"የአንድ ሰው ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝን ቅዋሜ በሀይል ለመደምሰስና የቡርዧውን በአንድ ቦታ አለመርጋት ለማሽመድመድ (ፓራላይዝ) ወዝአደሩ ከሰፊው ገበሬ መደብ ጋር ራሱን በማስተባበር የዲሞክራቲክ አብዮቱን ወደ ፍፃሜ ማድረስ አለበት ። የቡርዧውን ቅዋሜ በሀይል ለመደምሰስና የገበሬውንና የንኡስ ከበርቴውን ወላዋይነት ለማሽመድመድ ወዝአደሩ ከሰፊው መለስተኛ የወዝአደር ክፍሎች ጋር ራሱን በማስተባበር የሶሻሊስቱን አብዮት ማካሄድ አለበት ። አዲሶቹ ኢስክራይስቶች በክርክራቸውና በውሳኔዎቻቸው በሞላ ስለአብዮቱ ጠቅላላ ጉዞ እንዲያ ጠባብ አድርገው የሚያቀርቡት የወዝአደሩ ተግባር ግን እንዲህ ነው ። (ሌኒን ፤ ቅጽ ፩ ፡ ገጽ ፺፯ ይመልከቱ ።)

የቡርዧው አብዮት ወደ ወዝአደሩ አብዮት ስለ መተላለፉ ሌኒን በሁለት ታክቲኮች ላይ ከጻፈው ቀጥሎ ከፃፋቸውና በሌኒኒስት የአብዮት ቲዎሪ ውስጥ እንደ መሰረታዊነት ጥርት ብለው ከሚታዩት መጥቀሱ አያስፈልግም ።

አንዳንድ ጓዶች ሌኒን እንዲህ አይነቱ አስተሳሰብ ላይ የደረሰው በ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. እንደሆነና እስከዚያን ጊዜ

ድረስ ግን አብዮቱ በቡርዧ አጠቃላይ መዋቅር ውስጥ እንደሚቀር ፤ ከዚህም የተነሳ ስልጣን ከወዝአደሩና ከገበሬው የበላይ ገዥነት እጅ ወደ ቡርዧው እጅ እንጂ ወደ ወዝአደሩ እጅ አይገባም ብሎ ያስብ ነበር ብለው የሚያምኑ ይመስላሉ ። ይህ አባባል የኮሚኒስት የዜና ክፍላችን ውስጥ ድረስ እንኳን ገብቷል ይባላል ። ይህ አባባል ፍጹም ስህተትና ካለው ሀቅ ፍጹም የማይገጥም መሆኑን መጥቀስ የግድ ነው ።

ሌኒን በ፲፱፻፭ ዓ. ም. በተካሄደው የፓርቲው ጉባኤ ላይ ባደረገው ታዋቂ ንግግሩ ውስጥ የወዝአደሩንና የገበሬውን የበላይ ገዥነት ማለትም የዲሞክራቲክ አብዮትን አሸናፊነት የገለፀው "ሰላምና ፀጥታን በማደርጀት" በማለት ሳይሆን "ለጦርነት በመደራጀት" በማለት እንደሆነ ልገልጽ እችላለሁ ። (ቅጽ ፱ ፣ ገጽ ፪፻፷፬ ይመልከቱ ።)

በተጨማሪም "ስለ ጊዜያዊ መንግሥት" (፲፱፻፭) ከተፃፈው ታዋቂ ከሆነው ከሌኒን ፅሁፍ ለመጥቀስ እችላለሁ ። እዚህም ላይ በመካሄድ ላይ የነበረው የሩሲያ አብዮት ወደፊት ሊገጥሙት የሚችሉትን ሁኔታዎች በመዘርዘር "የሩሲያ አብዮት የጥቂት ወራት እንቅስቃሴ ሳይሆን የብዙ አመታት እንቅስቃሴ መሆኑን ፤ በስልጣን ላይ ካሉት ወገኖች ጥቃቅን ድሎች (ኮንሴሽንስ) ወደማግኘት ሳይሆን እነዚህን ስልጣን የያዙትን ራሳቸውን በጠቅላላ ወደ መገልበጡ እንዲያመራ ይህንንም እንዲያረጋግጥ" ለፓርቲው የስራ ድርሻ ይሰጣል ። እነዚህን የመጪውን ጊዜ ሁኔታዎች ሰፋ አድርጎ አውሮፓ ውስጥ ካለው አብዮት ጋር በማያያዝ እንዲህ ብሎ ይቀጥላል ።

"ይህንን ለማድረግ ከቻልን. . .የአብዮቱ ሰደድ ወደ መላው አውሮፓ ይዛመታል ። በቡርዧ አድህሪነት ስር የሚሰቃየው የአውሮፓ ሰራተኛም በተራው ይነሳና "እንዴት እንደሚደረግ" ያሳየናል ። ከዚያም በአውሮፓ ውስጥ ያለው አብዮታዊ ማእበል እንደገና ወደ ሩሲያ ይመጣል ፤ የጥቂት አብዮታዊ አመታት ዘመን የሆነውንም ወደ ብዙ አብዮታዊ አመታት ዘመን ይለውጠዋል ።. . ." (ቅጽ ፱ ፣ ገጽ ፩፻፲፱ ይመልከቱ ።)

በተጨማሪም በህዳር ወር ፲፱፻፲፭ ዓ. ም. የታተመውን የታወቀውን የሌኒን ፅሁፍ ልጠቅስ እችላለሁ ። እዚህም ላይ እንዲህ ብሎ ይፅፋል ።

"ወዝአደሩ እየታገለ ወደፊትም ስልጣንን አሸንፎ ለመያዝ ፤ ለሪፐብሊክ ፤ ለመሬት መወረስ ፤. . .ቡርዧ ሩሲያ ከወታደራዊ ፊውዳል "ኢምፔራያሊዝም" (ዛሪዝም) ለመላቀቅ በምታደርገው ትግል ወዝአደር ያልሆነው የሰፊው ህዝብ ክፍል ተሳታፊ እንዲሆን በቆራጥነት ይታገላል ። ወዝአደሩም የዚህን የቡርዧ ሩሲያን ከዛር አገዛዝ ፤ ከመሬት ከበርቴዎች ስልጣን መላቀቅ አመቺ ሁኔታ ለጥቅሙ በቶሎ[5] ይወስዳል ። ይህንንም የሚያደርገው ከገጠር ሰራተኛው ጋር በሚያደርገው ትግል ሀብታም ገበሬዎችን ለመርዳት ሳይሆን ከአውሮፓ ወዝአደሮች ጋር በመተባበር የሶሻሊስት አብዮትን ለማምጣት ነው ።" (ቅጽ ፲፰ ፣ ገጽ ፫፻፲፰ ይመልከቱ)

በመጨረሻም የወዝአደሩ አብዮትና ከሀዲው ካውትስኪ. ከሚለው መፅሀፉ ከታወቀው ክፍል

ለመጥቀስ እችላለሁ ። ስለሩሲያ አብዮት ጠቅላላ ጉዞ ሁለት ታክቲኮች ከተሰኘው ጽሁፉ ከላይ የተጠቀሰውን ጥቅስ በማስመልከት የሚከተለው ላይ ደርሶአል ።

"ሁኔታዎች ልክ እኛ ይሆናሉ እንዳልነው ሆኑ ። በአብዮቱ የተወሰደው ጎዳና የኛን አስተሳሰብ ትክክለኛነት አረጋግጦአል ። በመጀመሪያ "ከመላው" ገበሬ ጋር በዘውድ አገዛዝ ላይ በመሬት ከበርቴዎች ላይ በመካከለኛው ዘመን አገዛዝ ላይ ይነሳል ። (እስከዚህ ድረስ አብዮቱ ቡርዧ ዲሞክራቲክ ይሆናል ።) ከዚያም ከደሀው ገበሬ ከመለስተኛ ወዝአደሮችና በጠቅላላው ከተበዘበዙት ጋር ሆነን በካፒታሊዝም ላይ ፣ በገጠር ገበሬዎች ፤ ኩላኮች ፣ ትርፍ አግበስባሾች ላይ ይነሳል ፤ እስከዚህም ድረስ አብዮቱ ሶሻሊስት ይሆናል ። በመጀመሪያውና በሁለተኛው መሀከል የወዝአደሩ መዘጋጀት ምን ያህል እንደሆነና ከደሀ ገበሬዎች ጋር አንድነቱ ምን ያህል እንደሆነ ከሚያሳየው ደረጃ በስተቀር ሰው ሰራሽ (አርቲፊሻል) የቻይና ግንብ ለማቆም መሞከርና በሌላ ነገር ሁለቱን መለየት ማለት ማርክሲዝምን ከፋኛ ማወናበድ ፤ መደዴ ማድረግና በሊበራሊዝምነት መተካት ማለት ነው ።" (ቅጽ ፳፫ ፡ ገጽ ፴፱ ይመልከቱ ፡)

ይህ በቂ ይመስለኛል ።

ይህ ከሆነ ታዲያ ሌኒን "የቋሚ (የማያቋርጥ) አብዮትን" ሃሳብ ለምን ተቃወመ እንባል ይሆናል ።



ምክንያቱም ሌኒን የገበሬው አብዮታዊ ችሎታ (አቅም) "ይሚጠጥ" ፤ ዛሬገዝምን በፍጹም ለመደምሰስና ወደ ወዝአደራዊ አብዮት ለመሸጋገር የገበሬውን አብዮታዊ ሀይል እስከ መጨረሻው አቅሙ መጠቀም ያስፈልጋል ብሎ ሃሳብ ሲያቀርብ "የቋሚ አብዮት" ተከታዮች ግን በሩሲያ አብዮት ውስጥ የገበሬውን ከፍተኛ ሚና አልተረዱትም ፤ የገበሬውን አብዮታዊ ሀይልና የሩሲያ ወዝአደር ገበሬውን ለመምራት ያለውን ጥንካሬና ችሎታ ያቃልሉ ነበር ። በዚህም ገበሬውን ከቡርዧው ተፅዕኖ ስር የማላቀቁን ስራ ፤ ገበሬውን በወዝአደሩ ዙሪያ የማሰለፉን ስራ አደናቀፉ ።

ሌኒን ስልጣን ወደ ወዝአደሩ ተሸጋግሮ አብዮቱ ድል ይቀዳጅ ሲል "የቋሚ አብዮት" ተከታዮች ደግሞ በወዝአደሩ ስልጣን ወዲያውኑ መቋቋም ለመጀመር ፈለጉ ። ይህንንም ሲያደርጉ እንደገባርነት ቢጤ ስለሚቀረው ርዝራዥና "አነስተኛ ነገር" አይናቸውን በመጨፈን የሩሲያ ገበሬን ለመሰለ ታላቅ ሀይል ቦታም እንዳልሰጡት ሊረዱ አልቻሉም ። እንዲህ አይነቱም መመሪያ ገበሬውን በተባባሪነት ወደ ወዝአደሩ ማምጣትን ወደኋላ እንደሚጎትት አልተረዱም ።

ይህም በመሆኑ ሌኒን "የቋሚ አብዮት" ተከታዮችን የታገላቸው የማያቋርጥ በሚለው ጥያቄ ላይ ሳይሆን (ሌኒን ራሱ የማያቋርጥ የሚል አስተያየት ነበረውና) የወዝአደሩ ከፍተኛ ተባባሪ የሆነውን የገበሬውን ሚና በማቃለላቸው ፤ የወዝአደሩን የመሪነት ሃሳብ ሊረዱ ባለመቻላቸው ነበር ።

"የቋሚ አብዮት" ሃሳብ አዲስ ሃሳብ ተደርጎ መቆጠር የለበትም ። በመጀመሪያ የተሰነዘረው በ፲፰፻፵

አመታት ገደማ መጨረሻ ላይ (በ፲፰፻፸፭) ማርክስ ለኮሚኒስት ሊግ ባቀረበው ዝነኛ ንግግር (አድሬስ) ላይ ነው ። ከዚህ ፅሁፍ ነው "ቋሚ" አብዮተኞች የማያቋርጥ አብዮትን ሃሳብ የወሰዱት ። "ቋሚ" አብዮተኞቹ ከማርክስ የወሰዱትን ግን ለወጥ አድርገውታል ።

ኮሚኒስቶች አሸንፈው ሥልጣን እንዲያገኙ የሚያስገነዝባቸውን በዛ ያሉ አብዮታዊ ዲሞክራቲክ ጥያቄዎች ከዘረዘረ በኋላ ማርክስ በፅሁፉ ስለማያቋርጥ አብዮት የሚለው ይኸውና ።

"ዲሞክራቲካዊ ንኡስ ከበርቴዎች ከላይ የተጠቀሱት ጥያቄዎች የተቻሉት ያህል ተገኝተው አብዮቱ በተቻለ ፍጥነት እንዲያከትም ለማድረግ ሲፈልጉ አብዮቱን ቋሚ ወይንም የማያቋርጥ ማድረግ የኛ ፍላጎትም ተግባርም ነው ። ይህም ይብዛም ይነስ ንብረት ያላቸው መደቦች በሙሉ ከበላይነት አቋማቸው (ቦታቸው) በሀይል እስኪተወገዱ ድረስ ፤ ወዝአደሩ የመንግሥት ስልጣን እስኪጨብጥና የወዝአደሮች ህብረት በአንድ ሀገር ውስጥ ብቻ ሳይሆን በሁሉም ታላላቅ የአለም ሀገሮች ዳብሮ በእነዚህ ሀገሮች ወዝአደሮች መሀከል ያለው ውድድር ተወግዶና ቢያንስ ቢያንስ ወሳኝና ታላላቅ የሆኑ የምርት ሀይሎች በወዝአደሮች እጅ የተከማቹ እስኪሆኑ ድረስ ነው ።"

በሌላ አባባል ፦

ሀ. ማርክስ በ፲፰፻፵፱ አመታት ውስጥ የወዝአደሩ ስልጣን ወዲያውኑ የሚቋቋምበት አብዮት በጀርመን ውስጥ እንዲጀምር ፍጹም ሃሳብ አላቀረበም ። ከሩሲያ "ቋሚ" አብዮተኞች እቅድ ጋር የሚቃረን ነው ።

ለ. ማርክስ ያቀረበው ሃሳብ ስልጣን በወዝአደሩ ከተያዘ ደረጃ በደረጃ አንዱን የቡርዧ ክፍል ከሌላው እያከታተሉ ከስልጣን በማውረድ ወዝአደሩ የመንግሥት ስልጣን በመያዝ አብዮቱ የመጨረሻውን ድል እንዲቀዳጅ ብቻ ነበር ። በኢምፔሪያሊዝም ሁኔታዎች ስር ፤ በአብዮታችን ጉዞ ውስጥ የወዝአደሩ አብዮት ቲዮሪን በመከተል ማንኛውም ሌኒን ያስተማረውና ያካሄደው ሁሉ ከዚህ ሃሳብ ጋር ሙሉ በሙሉ ይገጥማል ።

ከዚህ የምናየው የሩሲያ "ቋሚ" አብዮተኞች በሩሲያው አብዮት ውስጥ የገበሬውን ሚናና ለወዝአደሩ መሪነት ሃሳብ የሚሰጠውን ከፍተኛ ግምት ከማቃለላቸውም በላይ የማርክስን "የቋሚ" አብዮት ሃሳብ በመለወጥ (በመጥፎ) ለተግባራዊ ጥቅም ተስማሚ እንዳይሆን አድርገውታል ።

ለዚህ ነው ሌኒን "የቋሚ" አብዮተኞችን ቲዮሪ "ጥንታዊና" "መልካም" ነው ብሎ በማንቋሸሽ ለምን ለአስር አመታት ያህል ሕይወት በዚህ መልካም ቲዮሪ መሀል እንዳለፈች ለማሰብ እንዳልፈለጉ በመጠየቅ ወቅሶአቸዋል ። (የሌኒን ፅሁፍ የቋሚ አብዮተኞች ቲዮሪ በሩሲያ ከወጣ ከአስር አመታት በኋላ በ፲፱፻፲፭ ዓ. ም. ነበር የተፃፈው ፤ ቅጽ ፲፰ ፡ ገጽ ፫፻፲፯ ይመልከቱ)

ለዚህ ነው ሌኒን ይህንን ቲዮሪ እንደ ግማሽ ሜንሼቪክ ቲዮሪ የቆጠረውና ይህ ቲዮሪ "ከቦልሼቪኮች

ወዝአደሩ በቁርጠኛንነት አብዮታዊ ትግል እንዲያካሂ
ድና የፖለቲካ ስልጣን እንዲይዝ የጠየቁትን እንደ
ወሰደና ከሜንሼቪኮች ደግሞ የገበሬውን ሚና "እንደ
ቀበልን" እንደወሰደ" የተናገረው ። (የሌኒንን የአብዮቱ
ሁለት መስመሮች ተመልከት ።)

ይህ ነው እንግዲህ የቡርዧው ዲሞክራቲክ አብ
ዮት ወደ ወዝአደራዊ አብዮት ስለማለፉና የቡርዧውን
አብዮት ወደ ወዝአደሩ አብዮት "በቶሎ" ለመሸጋገርያ
ስለመጠቀም ያለው የሌኒን ሃሳብ ።

እንቀጥል ። ድሮ አብዮቱ በአንድ ሀገር ድልን
መጎናፀፍ እንደማይችል ተደርጎ ይቆጠር ነበር ። ይህም
ግምት በቡርዧ ላይ ድልን ለመቀዳጀት የሁሉም ካለዚ
ያም ቢያንስ ቢያንስ የአብዛኛዎቹን በኢንዱስትሪ የገፉ
ሀገሮች ወዝአደሮች የተባበረ ድርጊት (አክሽን) ይጠይ
ቃል ከሚል የመጣ ነበር ። ካሁን ወዲያ ይህ አስተያየት
ካለው ሁኔታ ጋር አይገጥምም ። አሁን የዚህ አይነቱ
ድል ይቻላል ከሚል መነሳት አለብን ። ምክንያቱም
በኢምፔሪያሊዝም ሁኔታዎች ስር የልዩ ልዩ ካፒታሊ
ስት ሀገሮች በተለያየ ፍጥነት ማደግ ፤ በኢምፔሪያሊ
ዝም ውስጥ አደገኛ የሆኑ ቅራኔዎች ማደግና ወደ ጦር
ነት ማምራት ፤ በሁሉም የአለም ሀገሮች የአብዮታዊ
እንቅስቃሴዎች ማደግ ፤ ይህ ሁሉ በእያንዳንዱ ሀገር
ወዝአደሩ በየግሉ ድል ለማድረግ ወደመቻሉ ብቻ ሳይ
ሆን አስፈላጊ ወደ መሆኑም ነው የሚያመራው ። የሩ
ሲያ አብዮት ታሪክ የዚህ ቀጥተኛ ማረጋገጫ ነው ።
ይሁን እንጂ ቡርዧውን በተሳካ ሁኔታ ለመጣል የሚቻ
ለው አንዳንድ የግዴታ አስፈላጊ የሆኑ ሁኔታዎች በቅ
ድሚያ ሲኖሩ ብቻ መሆኑ መረሳት የለበትም ። እነዚህ
ሁኔታዎች ከሌሉ ግን ወዝአደሩ እንኳን ስልጣን ስለ
መያዙ ቀርቶ ስለስልጣን ማሰብ እንኳን አይቻልም ።



ስለነዚህ ሁኔታዎች "ግራ ክንፍ" ኮሚኒዝም
በሚለው መፅሀፉ ሌኒን የሚለው ይኸውና ፤

"በሁሉም አብዮቶችና በተለይም በሀያ
ኛው ክፍለ ዘመን ውስጥ በተካሄዱት በሶ
ስቱም የሩሲያ አብዮቶች የተረጋገጠው
የአብዮት መሰረታዊ ህግ እንደሚከተለው
ነው ። የተበዘበዘውና የተጨቆነው ሰፊ ህዝብ
በድሮው መንገድ ለመኖር የማይቻል መሆ
ኑን መረዳቱና ለውጥ መጠየቁ ለአብዮቱ
በቂ አይደለም ። በዝባገሮች በድሮው መን
ገድ ሊገዙና ሊኖሩ አለመቻላቸው ለአብ
ዮቱ አስፈላጊ ነው ። "የታችኛው መደቦች"
የድሮውን መንገድ ሳይፈልጉ ሲቀሩ ብቻና
"የላይኛው መደቦች" በድሮው መንገድ ሊቀ
ጥሉ ሳይችሉ ሲቀሩ ብቻ ፤ ያን ጊዜ ብቻ
ነው አብዮቱ ድል የሚጎናፀፈው ። ይህ እው
ነት በሌላ አባባልም ሊገለፅ ይቻላል ። ሀገር
አቀፍ ቀውስ ከሌለ አብዮት ሊሆን አይች
ልም ። (ሁለቱንም ፡ በዝባኛንም ተበዝባኛ
ንም ሲነካ ።)[7] ከዚህም ለአብዮቱ አስፈላጊ
የሚሆኑት በመጀመሪያ አብዛኛዎቹ ሰራተ
ኞች (ቢያንስ ቢያንስ የመደብ ንቃተ ህሊና
ያላቸው የሚያስቡ ፤ በፖለቲካ ንቁ ከሆኑ
ሰራተኞች አብዛኛዎቹ) አብዮቱ አስፈላጊ
ስለመሆኑ ሙሉ በሙሉ መረዳትና ለእሱም
ህይወታቸውን ለማሳለፍ መዘጋጀት አለባ
ቸው ። ሁለተኛው የገገርው መደቦችም ህይ
ወታቸውን ለመሰዋት የተዘጋጁ መሆን አለ

ባቸው ። በመጨረሻም የገገርው መደቦች እጅግ ወደኋላ የቀረውን ሰፊ ህዝብ እንኳን ወደ ፖለቲካ በሚስብ. . .መንግስቱን በሚያዳክምና አብዮተኞች በቶሎ ሊገለብጡት በሚያስችላቸው መንግስታዊ ቀውስ ውስጥ በማለፍ ላይ ያለ መሆን ይኖርበታል ። (ቅጽ ፳፩ ፣ ገጽ ፪፻፳፪ ይመልከቱ ።)

ነገር ግን በአንድ ሀገር የቡርዧው ከስልጣን መወገድና የወዝአደሩ ስልጣን መቋቋም ማለት ገና የሶሻሊዝም ፍጹም ድል መቀዳጀት ተረጋግጦአል ማለት አይደለም ። ስልጣኑን ካጠናከረና ገበሬውን በራሱ ምሳሌ ከመራው በኋላ ድልን የተጎናፀፈ ሀገር ወዝአደር ሶሻሊስት ህብረተሰብ መመስረት ይችላል ፤ መመስረትም አለበት ። ግን ይህን ማለት በዚህ አማካይነት ፍጹምና የመጨረሻ የሶሻሊዝም ድል ይጎናፀፋል ማለት ነው? ማለትም በአንድ ሀገር ሀይሎች ብቻ ሶሻሊዝምን ለማጠናከርና ሀገሪቱን ከውጪ ወረራና ብሎም የአሮጌው ስርአት እንደገና እንዳያንሰራራ የሚጠብቅ ዋስትና ሊሰጥ ይችላል? የለም አይችልም ። ለዚህ ቢያንስ ቢያንስ በብዙ ሀገሮች አብዮቱ ድልን እንዲቀዳጅ ያስፈልጋል ። ስለዚህ ለሌሎች ሀገሮች የአብዮት እድገት ሙሉ ድጋፍ መስጠት ድል የተጎናፀፈ አብዮት ትልቅ ተግባር ነው ። ስለዚህም በአንድ ሀገር ውስጥ ድልን የተጎናፀፈ አብዮት ራሱን እንደሚችል አካል አድርጎ መደላደል ሳይሆን እንደ ረዳ ፤ በሌሎች ሀገሮች ድሉን እንደሚያፋጥን አድርጎ ራሱን መቁጠር አለበት ።

ሌኒን ድልን የተጎናፀፈ አብዮት ተግባር "በሁሉም ሀገሮች ውስጥ ላለ አብዮት እድገት ፤ ድጋፍና



መነቃቃት በአንድ ሀገር ውስጥ ሊደረግ የሚቻለውን ሁሉ" ማድረግ ነው ብሎ ሲናገር ይህንን ሃሳብ በአጭሩ መግለጹ ነው ። (ቅጽ ፣ ፳፫ ፣ ገጽ ፫፻፹፯ ይመልከቱ።)

የሌኒኒስት የወዝአደር አብዮት ቲዮሪ መለያ ባህርይዎች ባጠቃላይ እነዚህ ናቸው ።

## ፬. የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት

ከዚህ ዋና ሀሳብ ሶስት መሰረታዊ አርእስቶችን እወስዳለሁ ።

ሀ. የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የወዝአደሩ አብዮት መሳሪያ ስለመሆኑ ፤

ለ. የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት በቡርዧው ላይ የወዝአደሩ አገዛዝ ስለመሆኑ ፤

ሐ. የሶቭየት ስልጣን የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የመንግሥት ቅርፅ ስለመሆኑ ፤

፩. የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የወዝአደሩ አብዮት መሳሪያ ስለመሆኑ ፤ የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ጥያቄ ከሁሉም በላይ የወዝአደሩ አብዮት ጥያቄ ዋና ይዘት ነው ። የወዝአደሩ አብዮት እንቅስቃሴው ፤ አላማውና ውጤቶቹ ስጋና ደም የሚያገኙት በወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ብቻ ነው ። የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የወዝአደሩ አብዮት መሳሪያ ፤ ልሳኑና ዋና ደጋፊው ሲሆን ህልውናውም መጀመሪያ የተወገዱትን በዝባዦች ቅዋሚ መደምሰስና የወዝአደሩን አብዮት የድል ውጤቶች ማጠናከር ፤ ሁለተኛም የወዝአደሩን አብዮት ወደፍፃሜው ማድረስ ፤ አብዮቱን ወደ ሶሻሊዝም ፍጹም ድል መጎናፀፍ ማድረስ ነው ። አብዮቱ ያለ

ወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ቡርዧውን ለማሸነፍና ስልጣኑን ለመገልበጥ ይችላል ። ነገር ግን በአንድ በተወሰነ በእድገት ደረጃው ላይ አብዮቱ አንድን ልዩ መሣሪያ እንደ ዋና ደጋፊው አድርጎ የበላይ ገዥነት ቅርፅ (ፎርም) ካልፈጠረ በስተቀር የቡርዧውን ቅዋሚ ለመደምሰስ ፣ ድሉን ጠብቆ ለማቆየትና ወደመጨረሻው የሶሻሊዝም ድል ለመግፋት አይችልም ።

“የማንኛውም አብዮት መሰረታዊ ጥያቄ የስልጣን ጥያቄ ነው” ። (ሌኒን) ይህ ሲባል ግን ተፈላጊው ጉዳይ ስልጣን መያዝና መጨበጥ ብቻ ነው ማለት ነው? አይደለም ። ስልጣን የመያዙ ጉዳይ የመጀመሪያው ብቻ ነው ። ከብዙ ምክንያቶች የተነሳ በአንድ ሀገር ውስጥ ከስልጣን የተወገደ ቡርዧ ከስልጣን ካስወገደው ወዝአደር ይበልጥ ሀይለኛ ሆኖ ለብዙ አመታት ይቆያል ። ስለዚህ የአብዮቱ ጠቅላላ አላማ ስልጣን ይዞ ለመቆየት ፤ ለማጠናከርና የማይበገር ለማድረግ ነው ። እዚህ ላይ ለመድረስ ምን ያስፈልጋል? እዚህ ላይ ለመድረስ ቢያንስ የወዝአደሩ አብዮት ድል ባደረገ ‘በማግስቱ’ የሚገጥሙትን ሶስት ዋና ዋና ተግባሮች ማካሄድ አስፈላጊ ነው ።

ሀ. በአብዮቱ ከስልጣን የተወገዱትንና ሀብታቸው የተወሰደውን የመሬት ከበርቴዎችንና የካፒታሊስቶችን ቅዋሚ መስበርና የካፒታል ሀይል እንዳያንሰራራ ለማድረግ የሚደረገውን ማንኛውንም ጥረት መደምሰስ ።

ለ. ሁሉንም ሰራተኛ ህዝብ በወዝአደሩ አካባቢ ለማሰለፍ ጥረት አድርጎ ማደራጀትና ይህንንም ስራ መደቦችን ለማስወገድና ለማጥፋት ወደ ሚያዘጋጅ መስመር ማካሄድ ።



ሐ. ከባእድ ጠላቶች ጋር ለሚያደርገው ትግል ፣ ከኢምፔሪያሊዝም ጋር ለሚያደርገው ትግል አብዮቱን ማስታጠቅ ፣ የአብዮቱን ሰራዊት ማደራጀት ።

እነዚህን ተግባሮች ለማካሄድና ለማስፈፀም የወዝአደሩ የባላይ ገዥነት ያስፈልጋል ።

“ከካፒታሊዝም ወደ ኮሚኒዝም ያለው ሽግግር አንድ ታሪካዊ ዘመንን ይወክላል ። ይህ ዘመን እስኪያበቃ ድረስም በዝባዦች የግዴታ የማንሰራራትን ተስፋ አጥብቀው ይንከባከቡታል ። ይህም ተስፋ ወደማንሠራራት ሙከራ ይተረጎማል ። ከመጀመሪያውም ከፉኛ መሸነፍ በኋላ የተወገዱት በዝባዦች ፤ (እኒያ ከስልጣን መወገዱን ለአንዳፍታም ያልጠረጠሩት ፣ ይቻላል ብለው ምንጊዜም ያልገመቱት፣ ይህን ሃሳብ ጭራሽ ያልተቀበሉት) አስር እጥፍ ባደገ ሀይል ፣ መቶ እጥፍ ባደገ ንዴትና ጥላቻቸው ፤ ይህንን የተነፈጉትን “ገነት” ለማስመለስ ራሳቸውን በጦርነቱ ውስጥ ያስገባሉ ። ይህንንም የሚያደርጉት እንደዚያ አይነት ጣፋጭና ቀላል ኑሮ ይኖሩ ለነበሩትና አሁን ግን ይህ “ስድ መንጋ” ውድቀትና ድህነትን (ወይንም “የጋራ” ሥራ . . .) ለፈረደባቸው ቤተሰባቸው ሲሉ ነው ። ከበዝባዥ ካፒታሊስቶች ጀርባም ሰፊው የንኡስ ከበርቴ ክፍል ይከተላል ። የብዙ ሀገሮች ታሪካዊ ልምድ ስለእነዚህ ሰዎች እንደሚመሰክረው ያወላውላሉ ፤ ያመነታሉ ። አንድ ቀን ከወዝአደሩ ጀርባ ይጓዛሉ ፣ በሚቀጥለው ደግሞ

በአብዮቱ ትግሮች ይደናገጣሉ ፤ በመጀመሪያው የሰራተኛው መሸነፍ ወይንም በመጠኑ መሸነፍ ብርክ ይይዛቸዋል ፤ ያለአንዳች ማመዛዘን ወዲያ ወዲህ ይቅበዘበዛሉ ። ራሳቸውን ደህና አስመስለው ያወራሉ ። ያማርራሉ። ካንዱ ካምፕ ወደሌላው ይሮጣሉ” ይላል ሌኒን ። (ቅጽ ፳፫ ፣ ገጽ ፫፻፶፭ ይመልከቱ ።)

ቡርዧውም የማንሰራራት ሙከራውን ለማድረግ የራሱ ምክንያት አለው ። ከተወገደ በኋላም ለብዙ አመታት ከስልጣን ካስወገደው ከወዝአደሩ ይበልጥ ሀይለኛ ሆኖ ስለሚቆይ ነው ።

ሌኒን “በዛ ባሉ ሀገሮች የአብዮቱ ባንድ ላይ ሊካሄድ የመቻሉ እድል በጣም አነስተኛ በመሆኑ አብዛኛውን ጊዜ የሚሆነው የአብዮቱ በአንድ ሀገር ማሸነፍ ስለሆነ በዝባዦች በአንድ ሀገር ብቻ ቢሸነፉ አሁንም ከተበዝባዦች የበለጠ ሀይለኛ ሆነው ይቆያሉ። (ቅጽ ፳፫ ፣ ገጽ ፫፻፶፬ ይመልከቱ ።)

ከስልጣን የተወገደው ቡርዧ ሀይሉ የት ላይ ነው?

በመጀመሪያ ፤ “በአለም አቀፍ ካፒታሊስት ሀይል ውስጥ ፤ በቡርዧው አለም አቀፍ ግንኙነቶች ጥንካሬና ለረዥም ጊዜ የመቆየት ሀይል ውስጥ” (ቅጽ ፳፭ ፣ ገጽ ፩፻፫)

ሁለተኛ ፤ እንደ እውነቱ ከሆነ “ከአብዮቱ በኋላ ለረዥም ጊዜ በዝባዦች የማይቀር ብዙ ተግባራዊ የሆኑ ጠቀሜታዎች (አድቫንቴጅስ) ይዘው ይቆያሉ ፤ አሁንም ቢሆን ገንዘብ አላቸው ፤ (ገንዘብን በጠቅላላው ባንዴ ለማጥፋት አይቻልም ።) ብዙውን ጊዜ አነስተኛ ተብለው የማይገመቱ አንዳንድ ተንቀሳቃሽ ንብረት አላቸው ። አሁንም ቢሆን ልዩ ልዩ ግንኙነቶች ፤ የድርጅትና የአመራር (ማኔጅመንት) ልምዶች ፤ አላቸው ። የሁሉንም አይነት የአመራር “ምስጢሮች” እውቀት (ልምዶች ፣ ዘዴዎች ፣ መንገዶችና ችሎታዎች) አሏቸው ። የተሻለ ትምህርት ፤ ከፍ ካሉ የልዩ ልዩ ስራ (ቴክኒካል) ሰራተኞች (እንደ ቡርዧው የሚኖሩና የሚያስቡ) ጋር የጠበቀ ግንኙነት አላቸው ። በጦር ስልት ከሌላ ጋር የማይወዳደርና እጅግ ከፍተኛ የሆነ ልምድ አላቸው ። (ይህ በጣም ጠቃሚ ነው ።) . . .ወዘተ. (ቅጽ ፳፫ ፣ ገጽ ፫፻፶፬ ይመልከቱ ።)

ሶስተኛ ፤ “በልማድ ሀይልና በአነስተኛ የማምረት ሀይል ውስጥ ። ምክንያቱም አሁንም ቢሆን አነስተኛ አመራረት በመላው አለም እጅግ በጣም የተስፋፋ ነው ። አነስተኛ አመራረትም በየቀኑ ፤ በየሰአቱ ፤ በሰፊው ካፒታሊዝምን ፤ ቡርዧውን ያመጣል ። . . .ምክንያቱም “መደቦችን ማጥፋት ማለት የመሬት ከበርቴዎችንና ካፒታሊስቶችን ብቻ ማባረር አይደለም ። ከሌላ ጋር ሲወዳደር እሱን በቀላሉ ልንፈፅም ችለናል ። አነስተኛ ሸቀጥ አምራቾችንም ማጥፋት ማለት ነው ። እነሱ ደግሞ ሊባረሩና ሊደመሰሱ

አይችሉም ። ከእነሱ ጋር በመግባባት መኖር አለብን ። እነሱን እንደገና ማስተማር እንደ ገና ማነፅ ይቻላል ። (መሆንም አለበት ።) ይህም የሚሆነው ከረዥም ዝግተኛና ጥንቃቄ ከተሞላበት የድርጅት ስራ በኋላ ብቻ ነው ።" (ቅጽ ፴፩ ፡ ገጽ ፩፻፹፫ ፡ ፩፻፹፱ ይመለልከቱ ።)

ስለዚህ ነው ሌኒን ፡—

"የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት በመገልበጡ ቅዋሚው አስር እጅ የሚጨምረው ፤ ይበልጥ ሀይለኛ ጠላት በሆነው በቡርዧው ላይ በአዲሱ መደብ የሚደረግ እጅግ ቁርጠኛና ርህራሄ የሌለው ጦርነት ነው . . . የወዝ አደሩ የበላይ ገዥነት በአሮጌው ህብረተሰብ ሀይሎችና ልማዶች ላይ የሚደረግ ሞገደኛ ትግል ነው ፤ በደምና ያለደም ፡ ሰላማዊና ሰላማዊ ያልሆነ ፤ ወታደራዊና ኢኮኖሚያዊ ፤ ትምህርታዊና አስተዳደር" የሚለው (ቅጽ ፴፩ ፡ ገጽ ፩፻፹፫ ፤ ፻፺ ይመልከቱ ።)

እነዚህን ተግባሮች በአጭር ጊዜ ውስጥ ለማካሄድ ፤ ይህን ሁሉ በጥቂት አመታት ውስጥ ለመፈፀም አነስተኛ የሆነ እድል እንኳን እንደሌለ እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ። ስለዚህ የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ፤ ከካፒታሊዝም ወደ ኮሚኒዝም የሚደረገው ሽግግር በቶሎ በሮ የሚያልፍ "የእጅግ አብዮታዊ" ድርጊቶችና ውሳኔዎች ጊዜ ተደርጎ መቆጠር የለበትም ። መቆጠር ያለበት እንደ አንድ የተሟላና ተከታ



ታይ የሆነ ታሪካዊ ዘመን ፤ በእርስ በርስ ጦርነቶችና የውጪ ግጭቶች የተሞላ ፤ ተስፋ መቁረጥ በሌለበት በማያቋርጥ የድርጅታዊ ስራና የኢኮኖሚ መገንባት ፤ ገፍቶ በመሄድና በማፈግፈግ ፤ በማሸነፍና በመሸነፍ እንደተሞላ ተደርጎ ነው ። ይህ ታሪካዊ ዘመን የሚያስፈልገው ለሶሻሊዝም ፍጹም ድል በቅድሚያ የሚያስፈልጉ የኢኮኖሚና የባህል ሁኔታዎችን ለመፍጠር ብቻ ሳይሆን ወዝአደሩ መጀመሪያ ራሱን እንዲያስተምርና ሀገራቱን ለማስተዳደር የሚበቃ ሀይል ሆኖ እንዲጠነክር ፤ ሁለተኛ የሶሻሊስት የምርት ድርጅት መካሄድን በሚያስተማምኑ መስመሮች ለመተለም እንዲያስችል ፤ የንኡስ ከበርቴውን ክፍል እንደገና ለማስተማርና እንደ ገና ለማነፅም ጭምር ነው ።

ማርክስ ለሠራተኞች እንዲህ ብሏል ፤

"አሁን ያሉትን ሁኔታዎች ለመለወጥ ብቻ ሳይሆን ራሳቸሁን ለመለወጥና የፖለቲካ ስልጣኑን ይዛችሁ ለመምራት ራሳችሁን ብቁ ለማድረግ በአስራ አምስት ፡ ሀያና ሀምሳ አመታት የርስ በርስ ጦርነቶችና ኢንተርናሽናል ግጭቶች ውስጥ ማለፍ አለባችሁ ።" (ካርል ማርክስና ፍሬድርክ ኢንግልስ ስራዎች ፤ ቅጽ ፩ ፡ ገጽ ፫፻፺፯) ።

ሌኒን የማርክስን ሃሳብ በመቀጠልና ይበልጥ በማዳበር እንዲህ ብሎ ፅፎአል ።

"በወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ስር በሚሊዮን የሚቆጠሩ ገበሬዎችን፤ አነስተኛ ባለንብረቶችን፣ በመቶ ሺህ የሚቆጠሩ የቢሮ ሰራተኞችን ፤ ባለስልጣኖችንና የቡርዧ ምሁራንን እን

ደገና ማስተማር አስፈላጊ ይሆናል ። ይህም የሚደረገው ሁሉም ለወዝአደሩ መንግስትና ለወዝአደሩ አመራር የበታች እንዲሆኑ ፤ ከቡርዧ ልማዳቸውና ወጋቸው እንዲላቀቁ ለማድረግ ነው ። እንደዚሁም ደግሞ "በወዝአደሩ የበላይ ገዥነት መሰረት ላይ. . . ወዝአደሮች ራሳቸውን እንደገና እንዲያስተምሩ ረዥም ትግል ማካሄድ አለብን ። ወዝአደሮች የንኡስ ከበርቴ ኢምህ አልቦአቸውን (ፕሬጁዲስስ) በተአምር ፤ በድንግል ማርያም ትእዛዝ ፣ በመፈክር ፣ በውሳኔና በአዋጅ ትእዛዝ ባንድ ጊዜ አይለቁም ። የሚለቁት በሰፊው የንኡስ ከበርቴ ተፅዕኖዎች ላይ በሚደረገው በረዥምና አስቸጋሪ በሆነው በሰፊ የትግል ጉዞ ውስጥ ነው ። (ቅጽ ፳፭ ፣ ገጽ ፪፻፵፯ ፣ ፪፻፵፰ ይመልከቱ ።)

፱. የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት በቡርዧው ላይ የወዝአደሩ አገዛዝ ስለመሆኑ ፤ እስከአሁን ካየነው የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የድሮውን የኢኮኖሚና የፖለቲካ ስርአት የሚተው ፤ በአገዛዝ ውስጥ የሚደረግ የግለሰቦች ለውጥ ፤ "የካቢኔ ለውጥ ፤ ብቻ እንዳልሆነ ግልፅ ነው ። የበላይ ገዥነትን እንደ እሳት የሚፈሩትና በፍርሀታቸውም "ስልጣን መያዝ" የሚለውን ፅንሰ ሀሳብ የበላይ ገዥነት በሚለው ፅንሰ ሃሳብ ቦታ የሚተኩ የሁሉም ሀገር ሜንሼቪኮችና አድርባዮች ብዙውን ጊዜ "ስልጣን መያዝን" ወደ ካቢኔ ለውጥ ፤ እንደእነ ሼይድማንና ኖልክ ፣ ማክዶናልድና ሂንደርሰን አዲስ ሚኒስትር ስልጣን ላይ ወደ መውጣቱ ዝቅ ያደርጉታል ። እነዚህና ተመሳሳይ የካቢኔ ለውጦች ከወዝአደሩ የበላይ



ገዥነት ፣ እውነተኛው ስልጣን በእውነተኛው ወዝአደር ከመያዙ ጋር ምንም ግንኙነት እንደሌላቸው መግለጹ እስከዚህም አስፈላጊ አይደለም ። እንደነ ማክዶናልድና ሼይድማን አይነቶች ስልጣን ላይ ሆነው የድሮው ቡርዧ ስርአት እንዲኖር ሲፈቅዱ ፣ የእነሱ አገዛዝ ቡርዧውን የሚያገለግል መሳሪያ ፤ የኢምፔሪያሊዝምን ነቀርሳ የሚደብቅ ከለላ ፤ የተበዘበዘውንና የተጨቆነውን ሰፊ ህዝብ አብዮታዊ እንቅስቃሴ ለመቃወም በቡርዧው እጅ ያለ መሳሪያ ሆኖ ከማገልገል ሌላ ምንም ሊሆን አይችልም ። ያለከለላ ድጋፍ ሰፊውን ህዝብ ለመጨቆንና ለመበዝበዝ የማያመች አስቸጋሪና ትርፍ የሌለው ሆኖ ሲያገኝ ካፒታል እንደነዚህ ያሉትን አገዛዞች ይፈልጋል ። እንደነዚህ አይነት አገዛዞች ሲታዩ "እዚያ" (ካፒታሊስት ካምፕ) "በሺፕካ መተላለፊያ"[8] ሁሉ ነገር ጤናማ እንዳልሆነ ምልክት ነው ። ያም ሆነ ይህ እንዲህ አይነቶች አገዛዞች የግዴታ በከለላ ስር የሚኖር ካፒታል መንግስቶች ሆነው ይቀራሉ ። ሰማይ ከመሬት የሚርቀውን ያህል ነው የማክዶናልድ ወይንም የሼይድማን አገዛዝ ከወዝአደሩ ስልጣን መያዝ የሚርቁት ። የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የአገዛዝ ለውጥ አይደለም ። በማእከላዊውም ሆነ በቀበሌ አዲስ የስልጣን መዋቅሮች ያሉት አዲስ መንግስት ነው ። በድሮው መንግስት ፤ በቡርዧው መንግስት ፍርስራሽ ላይ የተገነባ የወዝአደሩ መንግስት ነው ።

የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የሚገነባው በቡርዧው ስርአት መሰረት ላይ ሳይሆን ስርአቱ በመንኮታኮት ላይ ሳለ ፤ ቡርዧው ከተወገደ በኋላ ፣ የመሬት ከበርቴዎችና ካፒታሊስቶች በመወረስ ላይ እያሉ ፤ ዋና ዋና የማከናወኛ መሳሪያዎችና የምርት መገልገያዎች ህብረተሰባዊ በመደረግ ላይ ሳሉ ፤ ሀይለኛ የወዝአደር አብ

ዮት በመካሄድ ላይ በሚገኝበት ጊዜ ነው ። የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት በቡርዧው ላይ ሀይልን በመጠቀም የተመሰረተ አብዮታዊ ስልጣን ነው ።

መንግስት በገዥው መደብ እጅ ያለና የመደብ ጠላቶቹን ቅዋሜ ለማፈን ገዥው መደብ የሚጠቀምበት መሳሪያ ነው ። በዚህ ረገድ የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት በመሰረቱ ከሌላው መደብ የበላይ ገዢነት አይለይም ። ምክንያቱም የወዝአደሩ መንግሥትም ያው ቡርዧውን መጨቆኛ መሳሪያ ነው ። ነገር ግን አንድ ከፍተኛ ልዩነት አለ ። ይህም ልዩነት ያለው እስከ ዛሬ ድረስ የነበሩ የመደብ መንግስቶች ሁሉ ብዙሀን በሆኑ ህዝቦች ላይ በዝባዥ የሆኑ ንኡሳን የሚያካሄዱት የበላይ ገዥነት ስለነበረ ነው ። የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ግን ይበዘብዙ በነበሩ ንኡሳን ላይ ይበዘበዙ የነበሩ ብዙሃን የሚያደርጉት የበላይ ገዥነት ነው ።

በአጭሩ ፡—

"የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት በቡርዧው ላይ የወዝአደሩ አገዛዝ በህግ የማይወሰን ፤ በሀይል ላይ የተመሰረተ አገዛዝ ነው ። ይህም አገዛዝ የተበዘበዘውና የለፍቶ አዳሪው ሰፊ ህዝብ ድጋፍ አለው ።" (ሌኒን መንግስትና አብዮት)

ከዚህም ሁለት ዋና ዋና ማጠቃለያዎች ይከተላሉ ።

የመጀመሪያው ማጠቃለያ ፤ የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት "የተሟላና የሁሉም የሆነ" ዲሞክራሲ ፣ ማለትም ዲሞክራሲ ፣ ለህብታምም ለደሀም ሊሆን አይችልም ። የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት በአዲስ መንገድ



ዲሞክራታዊ የሆነ መንግስት መሆን አለበት ። (ለወዝአደሮችና ባጠቃላይ ንብረት አልባ ለሆኑት)[9] እንዲሁም በአዲስ መንገድ የበላይ ገዥ (ዲክታቶርያል) መሆን አለበት ። (በቡርዧው ላይ)"[10] (ቅጽ ፳፩ ፣ ገጽ ፫፻፺፫ ይመልከቱ፡) ስለሁለንታዊ እኩልነት ፣ ስለ "ንጹህ" ዲሞክራሲ ፣ ስለ "ፍጹም የሆነ" ዲሞክራሲና የመሳሰሉት የካዎቲስኪና ደቀመዝሙሮቹ ወሬ በበዝባዥና በተበዝባዥ መሀከል እኩልነት ፍጹም የማይቻል የመሆኑ የማይታበል ሀቅ የቡርዧዎች መደባበቂያ ዘዴ ነው ። "የንጹህ" ዲሞክራሲ ቲዮሪ በኢምፔሪያሊስት ዘራፊዎች የተደለለውና በእነሱም የሚቀለበው የስራተኛው መደብ ድሎተኛና የላይኛው ክፍል ቲዮሪ ነው ። የመጣውም የካፒታሊዝም ነቀርሳዎችን ለመሸፈን ፤ ኢምፔሪያሊዝምን ቀባብቶ ለማስማመርና ከተበዘበዘው ሰፊ ህዝብ ጋር በሚያደርገው ትግል የሞራል ድጋፍ ለመስጠት ነው ። በካፒታሊዝም ስር ለተበዝባዥ ምንም አይነት እውነተኛ "ነፃነት" የለም ። ሊኖርም አይችልም ። ሌላው ቢቀር የማተሚያ መሳሪያዎች ፤ መሥሪያ ቤት ፣ ወረቀት. . . ወዘተ. "ነፃነትን" ለመጠቀም አስፈላጊ እንደመሆናቸው የበዝባገሮች ልዩ መብት (ፕሪቨሌጅ) በመሆናቸው አይኖርም ። በካፒታሊዝም ስር የተበዘበዘው ሰፊ ህዝብ ሀገሪቱን በማስተዳደር ውስጥ አይካፈልም ፤ ምንጊዜም ደግሞ ሊካፈል አይችልም ። ሌላው ቢቀር እጅግ ዲሞክራታዊ በሆነ አገዛዝ እንኳን በካፒታሊዝም ሁኔታዎች ስር አገዛዝ በህዝብ አይቋቋምም ፤ እንደ ሮዝቻይልድ ፣ ስቲንስ ፣ ሮክፌለርና ሞርጋን ባሉት እንጂ ። በካፒታሊዝም ስር ያለ ዲሞክራሲ የካፒታሊስት ዲሞክራሲ ፣ የጥቂት በዝባገሮች ዲሞክራሲ ነው ። የሚመሰረተውም የተበዝባዥ ብዙሀንን መብቶች በመወ

ሰንና ወደነሱም በማተኮር ነው ። በወዝአደሩ
ገዥነት ስር ብቻ ነው ለተበዘበዙት እውነተኛ የበላይ
ሊኖርና ወዝአደሮችና ገበሬዎች ሀገሪቱን ነፃነት
በኩል እውነተኛ ተሳትፎ ሊኖራቸው በማስተዳደር
ዝአደሩ የበላይ ገዥነት ስር ዲሞክራሲ የሚችለው ። በወ
ዲሞክራሲ ነው ፤ የተበዘበዙ ብዙሃን ዲሞክራሲ የወዝአደሩ
የሚመሰረተውም ይበዘብዙ የነበሩ የጥቂቶቹን ነው ፤
በመወሰን ወደነዚህም በማተኮር ላይ ነው ። መብት

ሁለተኛ ማጠቃለያ ፤ የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት
ከቡርዧ ህብረተሰብና ከቡርዧ ዲሞክራሲ ከሰላማዊ የእድ
ገት ውጤት ሊገነባ አይችልም ። ሊገነባ የሚችለው የቡር
ዧውን የመንግስት መዘውር የቡርዧውን ጦር ፣ የቡር
ዧውን የቢሮክራሲ ማካሄጃና የቡርዧውን ፖሊስ ካን
ኮታኮተ በኋላ ብቻ ነው ።

ማርክስና ኤንግልስ በኮሚኒስት ማኒፌስቶ መግ
ቢያ ውስጥ ፤

“የሰራተኛው መደብ ተዘጋጅቶ የተቀመጠን
የመንግስት መዘውር (ማሺነሪ) ዝም ብሎ
ወስዶ ለራሱ ጉዳይ ሊጠቀምበት አይችልም”
ይላሉ ። በወዝአደሩ አብዮት ተግባር ማር
ክስ ለኩግልማን በ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. በጻፈው
ደብዳቤው እንዲህ ይላል ፤ “. . . ካሁን
ወዲያ እንደበፊቱ ቢሮክራሲያዊ መዋቅ
ሩን ካንዱ እጅ ወደ ሌላው ማዛወር
ሳይሆን ማንኮታኮት ነው ። . . . በአህጉሩ
ላለው ለማንኛውም እውነተኛ ህዝባዊ
አብዮት በቅድሚያ አስፈላጊ የሚሆነው
ሁኔታ ይህ ነው ።”



በየሀገሩ ያሉ ሚንሼቪኮችና አድርባዮች ማርክስ
ቢያንስ ቢያንስ ከአውሮፓ አህጉር ውጪ በሌላ ሀገ
ሮች (ለምሳሌም አሜሪካ ፣ ብሪታንያ) ቡርዧ ዲሞክ
ራሲ ወደ ወዝአደራዊ ዲሞክራሲ ሰላማዊ በሆነ
መንገድ ሊለወጥ ይቻላል በማለት ቆጥቦ (ኳሊፋይንግ)
ያቀረበውን ሐረግ ሙሉ በሙሉ ተቀብሎታል ብለው
እንዲጮሁ ሰበብ ሆኖአቸዋል ። በርግጥም ማርክስ ይህ
ሊሆን መቻሉን ተቀብሎታል ። ብሪታንያንና አሜሪካንን
በሚመለከተው ረገድ በ፲፰፻፸ ውስጥ ይህን የተቀበለ
በት በቂ የሆነ ምክንያት ነበረው ። ያኔ ሞኖፖሊዝምና
ኢምፔሪያሊዝም አልነበሩም ነበር ። እነዚህም ሀገ
ሮች ከእድገታቸው ልዩ ሁኔታ የተነሳ ገና የዳበረ ወታ
ደራዊነትና (ሚሊታሪዝም) ቢሮክራሲ አልነበራቸውም
ነበር ። የዳበረ ኢምፔሪያሊዝም ከመምጣቱ በፊት ሁኔ
ታው እንደዚህ ነበር ። ግን ከሰላሳና አርባ አመት በኋላ ፤
በእነዚህ ሀገሮች ያለው ሁኔታ ስር ነቀል ለውጥ ካደ
ረገ ፣ ኢምፔሪያሊዝም ካደገና ሁሉንም ካፒታሊስት
ሀገሮች ካቀፈ ፣ ወታደራዊነትና ቢሮክራሲም እንዲሁ
በአሜሪካንና በብሪታንያ ከታዩ ለሰላማዊ እድገት
የነበሩት ልዩ ሁኔታዎች በብሪታንያና በአሜሪካ ከጠፉ ፤
ከእንግዲህ እነዚህን ሀገሮች በሚመለከተው ረገድ
የተደረገው መቆጠብ ካሁን ወዲያ የግድ ሊሠራ ይች
ላል አይባልም ።

“ዛሬ በ፲፱፻፲፯ ዓ.ም. በመጀመሪያው ታላቁ
የኢምፔሪያሊስት ጦርነት ዘመን ይህ በማር
ክስ የተደረገው መቆጠብ ካሁን ወዲያ አይ
ሰራም ። ሁለቱም ማለት አሜሪካና ብሪታንያ
ታላቆቹና የመጨረሻዎቹ (በመላው አለም)
የእንግሎ ሳክሰን “ነፃነት” ወኪሎች ማለ

ትም ምንም ወታደራዊነትና ቢሮክራሲ ያል
ነበራቸውና አሁን ግን ማንኛውንም ነገር
ከራሱ ስር በሚያደርግ ሁሉንም ነገር እግሩ
ስር በሚረግጠው በአውሮፓ ቢሮክራሲያዊ
ወታደራዊ ተቋሞች ቆሻሻና የደም ረግረግ
ውስጥ ሙሉ በሙሉ የሰመጡ ናቸው ። ዛሬ
በሁለቱም ማለትም በአሜሪካም በብሪታን
ያም የማንኛውም እውነተኛ አብዮት ተቀ
ዳሚ የሚሆነው ተግባር ተዘጋጅቶ የተቀመ
ጠውን የመንግሥት መዘውር ማንኮታኮትና
መደምሰስ ነው ። (በእነዚህ ሀገሮች ከ፲፱፻፲፬
እስከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ድረስ እስከ "አውሮፓ
ውያን" አጠቃላይ የኢምፔሪያሊስት ደረጃ
የተጠናቀቀውንና ተዘጋጅቶ የተቀመጠውን
(ሬዲ ሜድ) የመንግሥት መዘውር ማንኮታ
ኮትና መደምሰስ ነው ። (ሌኒን ፡ ቅጽ ፳፭ ፡
ገጽ ፫፻፺፭ ይመልከቱ ።)

በሌላ አነጋገር ሰላማዊ ያልሆነ (ቫዮለንት) የወ
ዝአደሩ አብዮት ህግ ፡ እንደዚህ ላለው አብዮት በቅድ
ሚያ አስፈላጊ የሚሆነው የቡርዧውን መንግሥት
መዘውር የማንኮታኮት ህግ ፡ በአለም ኢምፔሪያሊስት
ሀገሮች የግዴታ የማይቀር የአብዮታዊ እንቅስቃሴ ህግ
ነው ።

ወደፊትም በታላላቆቹ ካፒታሊስት ሀገሮች ወዝ
አደሩ ድል ካደረገ ፡ የአሁኑ የካፒታሊስት ከበባ (ኢንሰ
ርከልመንት) በሶሻሊስት ከበባ ከተለወጠ ፡ "ሰላማዊ"
ጎዳና የሚቻል ይሆናል ። ምክንያቱም አንዳንድ ካፒ
ታሊስት ሀገሮች የአለምን "አመቺ ያልሆነ" ሁኔታ
ሲመለከቱ ለወዝአደሩ ከፍተኛ የሆኑ ድሎችን (ኮንሲ



ሽንስ) "በፈቃዳቸው" መልቀቁን አመቺ አድርገው
ሊቆጥሩት ይችላሉ ። ይሁንና ይህ አባባል (ሳፖዚሽን)
የሚሰራው ከዛሬ ብዙ አመታት በኋላና የሚያሳየውም
ያኔም ቢሆን ሊሆን መቻሉን ነው ። የወደፊቱን ቅርብ
ጊዜ በሚመለከት ረገድ ግን ለእንዲህ አይነቱ ምንም
በቂ ምክንያት የለም ። ስለዚህ ሌኒን የሚከተለውን ሲል
ትክክል ነበር ።

"የቡርዧው የመንግሥት መዘውር በሀይል
ካልተንኮታኮተና በእሱ ቦታ አዲስ ካልተ
ተካ የወዝአደሩ አብዮት ፍጹም ሊሳካ አይች
ልም ። (ቅጽ ፳፫ ፡ ገጽ ፪፻፴፪ ይመልከቱ ።)

፫. የሶቭየት ስልጣን የወዝአደሩ የበላይ ገዥ
ነት መንግስት ስለመሆኑ ።

የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት የሚያመለክተው
የቡርዧውን መታፈን ፡ የቡርዧውን የመንግሥት መዘ
ውር መንኮታኮትና በቡርዧ ዲሞክራሲ ቦታ የወዝ
አደሩ ዲሞክራሲ መተካቱን ነው ። ይህ ግልጽ ነው ።
ነገር ግን በምን የድርጅቶች ዘዴ ነው ይህ ታላቅ ስራ
የሚካሄደው? በቡርዧ የፓርላማ ዘዴዎች መሰረት
ላይ ያደጉት የድሮዎቹ አይነት የወዝአደሩ ድርጅቶች
እንደሆኑ ለዚህ ተግባር በቂ አይደሉም ። በዚህ ላይ
ምንም ያህል ጥርጥር ሊኖር አይችልም ። እንግዲያው
የቡርዧው የመንግሥት መዘውር (ማሺን) መቃብር
ቆፋሪ በመሆን የሚያገለግል ፡ ይህን መዘውር የሚሰባ
ብርና በቡርዧው ዲሞክራሲ ቦታ የወዝአደሩን ዲሞክ
ራሲ የሚተካ ብቻ ሳይሆን የወዝአደሩን የመንግስት
ስልጣን መሰረትም ለመጣል የሚችል አዲስ የወዝአ
ደሩ ድርጅት ቅርጾች ምንድን ናቸው?

ይህ የወዝአደሩ ድርጅት አዲስ ቅርጽ ሶቭየቶች ናቸው ።

ከድሮው የድርጅት ቅርጾች ጋር ሲወዳደር የሶቭየቶች ሀይል ምኑ ላይ ነው?

እንደ እውነቱ ከሆነ እጅግ አጠቃላይ የሆኑ የወዝአደሩ የብዙሀን ድርጅቶች ሶቭየቶች ናቸው ። ምክንያቱም አንድም ሳያስቀሩ ሰራተኞችን በሙሉ የሚያቅፉ እነሱ ብቻ ናቸው ።

ሁሉንም የተጨቆኑና የተበዘበዙ ሰራተኞች ገበሬዎች ፡ ወታደሮችና መርከበኞች አንድ የሚያደርጉ ፤ ከዚህም የተነሳ የሰፊው ህዝብ ግንባር ቀደም የሆነው ወዝአደሩ የሰፊው ህዝብ ትግል የፖለቲካ መሪነቱን ተግባር እጅግ በቀላሉና በተሟላ አኳኋን ሊያካሂድ የሚያስችሉት የብዙሀን ድርጅቶች እነሱ ብቻ በመሆናቸው ነው ።

ሶቭየቶች የሰፊው ህዝብ አብዮታዊ ትግል ልሣን የሰፊው ህዝብ የፖለቲካ ድርጊቶች ፡ የሰፊው ህዝብ አመፅ እጅግ ሀይለኛ የሆኑ ልሳኖች — የፋናንስ ካፒታልን ወሰን የለሽ ሀያልነትና ተቀጥላዎቹን ለመሰባበር የሚችሉ መሳሪያዎች — በመሆናቸው ነው ።

ሶቭየቶች የራሱ የሰፊው ህዝብ በቅርቡ ያሉለት ድርጅቶች በመሆናቸው ነው ። ማለትም እጅግ ዲሞክራሲያዊና ከሰፊው ህዝብ ድርጅቶች እጅግ ተሰሚ የሆነው ። ይህም አዲሱን መንግስትና አስተዳደሩን በመገንባት ውስጥ እጅግ ከፍተኛ የሆነ አመቺ ያደርጋል ። ይህም ደግሞ የድሮውን ስርአት ለመደምሰስና ለአዲሱ ወዝአደራዊ ስርአት በሚደረገው ትግል የሰፊውን ህዝብ



አብዮታዊ ሀይል ፡ ታታሪነትና የመፍጠር ችሎታ በተሟላ አኳኋን በተግባር ላይ እንዲውል ያደርጋል ።

የሶቭየት ስልጣን የቀበሌ ሶቭየቶች በአንድ የጋራ የመንግስት ድርጅት ስር መዋሀድ ነው ፤ የሶቭየቶች የተጨቆነውና የተበዘበዘው ሰፊ ህዝብ እንደ ግንባር ቀደምትነት ፡ እንደ ገዥ መደብነት በወዝአደሩ መንግስት ድርጅት ውስጥ መዋሃድ ነው ። የነዚህ የቀበሌ ሶቭየቶች በአንድ የሶቭየቶች ሪፑብሊክ ውስጥ መዋሀድ ነው ።

የሶቭየት ስልጣን ዋና ቁምነገሩ የእነዚህ በካፒታሊስቶችና በመሬት ከበርቴዎች የተበዘበዙ መደቦች እጅግ አጠቃላይና እጅግ አብዮታዊ የሆኑ የብዙሀን ድርጅቶች አሁን የመንግስቱ ጠቅላላ ስልጣን ፡ የመንግስት ጠቅላላ መሳሪያ ፡ (አፓራተስ) “ቋሚና ብቸኛ” መሰረት በመሆናቸው “እጅግ ዲሞክራታዊ በሆኑ ቡርዧ ሪፑብሊኮች እንኳን” በህግ በኩል እኩል ናቸው እየተባለ “እንደ እውነቱ ግን በልዩ ልዩ አሻጥሮችና የተንኮል ዘዴዎች በፖለቲካ ኑሮ ውስጥ እንዳይሳተፉና የዲሞክራቲክ መብቶችና ነፃነቶችን እንዳይጠቀሙ የተከለከሉት የሰፊው ህዝብ ወገኖች አሁን ያለጥርጥር የማያቋርጥና ይበልጡንም ወሳኝ በሆነ በመንግስቱ ዲሞክራታዊ አስተዳደር ውስጥ ለመሳተፍ”[11] እመቻላቸው ላይ ነው ። (ቅጽ ፳፬ ፡ ገጽ ፲፫ ሌኒንን ይመልከቱ ።)

ለዚህ ነው የሶቭየት ስልጣን ከአሮጌው ቡርዧ ዲሞክራታዊና ፓርላማዊ አይነት መርህ የሚለይ አዲስ አይነት (ፎርም) የመንግስት ድርጅት የሆነው ። ይህም አዲስ አይነት መንግስት ሰርቶ አዳሪውን ሰፊ ህዝብ ለመበዝበዝና ለመጨቆን ተግባር ሳይሆን ከማንኛውም

አይነት ብዝበዛና ጭቆና ሙሉ በሙሉ አርንት ለማውጣት የሚውል የወዝአደሩን የበላይ ገዥነት የመቀበል ተግባር ነው ።

ሌኒን በሶቭየት ስልጣን መምጣት “የቡርዧ ዲሞክራቲክ ፓርላማዊነት ዘመን አብቅቶ አዲስ የአለም ታሪክ ምእራፍ ማለትም የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ዘመን ተከፍቷል” ያለው ትክክል ነው ።

የሶቭየት ስልጣን መለያ ባህርይ ያለው ምን ላይ ነው?

መደቦች እስካሉ ድረስ ከሚኖሩ ልዩ ልዩ ድርጅቶች ሁሉ እጅግ አጠቃላይና እጅግ ዲሞክራታዊ ሊሆን የሚችል ስልጣን እመሆኑ ላይ ነው ። ምክንያቱም በበዝባዦች ላይ በሚያደርጉት ትግል በሰራተኞችና በተበዘበዙ ገበሬዎች መሀከል የመተሳሰርና የመተባበር መድረክ በመሆኑና ራሱን በዚህ መተሳሰርና መተባበር ስራ ላይ በመመስረቱ የሶቭየት ስልጣን በንኡሳኑ ህዝብ ላይ የብዙሀኑ ህዝብ ስልጣን ነው ። የበላይነቱ መግለጫ ፣ የብዙሀኑ መንግስት ነው ።

በመደብ ህብረተሰብ ውስጥ የሶቭየት ስልጣን ከሁሉም የመንግስት ድርጅቶች የበለጠ ብሔር አቀፍ (ኢንተርናሽናል) በመሆኑ ነው ። ምክንያቱም ማንኛውንም አይነት የብሔር ጭቆና በመደምሰስና በልዩ ልዩ ብሔረሰቦች ለፍቶ አደር ህዝቦች ትብብር ላይ በመመስረቱ የእነዚህን ህዝቦች በአንድ መንግስት ህብረት ውስጥ መዋሀድ የቀለለ ያደርገዋል ።

የሶቭየት ስልጣን መዋቅር ራሱ የተጨቆነውንና የተበዘበዘውን ሰፊ ህዝብ የመምራቱን ተግባር ፣ የዚህ ህዝብ ግንባር ቀደም የሆነውን የወዝአደሩን ተግባር



በማቅለል ከሶቭየቶች ውስጥ በፖለቲካ እጅግ ንቃተ ህሊና ያለው ማእከላዊ ቦታ ያደርገዋል ።

> “የሁሉም አብዮቶችና የሁሉም የተጨቆኑ መደቦች እንቅስቃሴዎች ፣ ልምድ ፣ የአለም ሶሻሊስቶች እንቅስቃሴ ልምድ የሚያስተምረን የተበታተነውንና ወደኋላ የቀረውን የለፍቶ አዳሪውንና የተበዘበዘውን ህዝብ ክፍል ሊያስተባብርና ሊመራ የሚችል ወዝአደሩ ብቻ መሆኑን ነው ።” (ቅጽ ፳፱ ፣ ገጽ ፲፱ ይመልከቱ ።)

እዚህ ላይ ቁምነገሩ የሶቭየት ስልጣን መዋቅር ከተጠቀሰው ልምድ የተገኘውን ትምህርት በተግባር ላይ ማዋልን ቀላል ማድረጉ ነው ።

የሶቭየት ስልጣን የህግ አውጪነትንና የህግ አስፈፃሚነትን ስልጣን በአንድ የመንግስት ድርጅት ውስጥ በማዋሀድና በግዛት ድንበር የሚወሰኑ የምርጫ (መራጭ) አካባቢዎችን ራሳቸውን በቻሉ በፋብሪካ ፣ በኢንዱስትሪ ክፍሎች በመተካት በዚያውም ሰራተኞችንና ባጠቃላይ ለፍቶ አዳሪውን ሰፊ ህዝብ ከመንግስት አስተዳደር ማካሄጃ መሳሪያ (አፓርተስ) ጋር በቀጥታ በማገናኘት እንዴት አድርገው ሀገሪቱን እንደሚያስተዳድሩ ስለሚያስተምራቸው ነው ።

ጦር ሀይሉን ካለበት ከቡርዧ ትእዛዝ ስር አላቆ በቡርዧ ስርአት ስር ከነበረው ከህዝብ መጨቆኛ መሳሪያነት ህዝቡን ከሀገር ውስጥም ሆነ ከባእድ ቡርዧ ቀንበር ወደሚያላቅቅ መሳሪያነት ለመለወጥ የሚችል የሶቪዬት ስልጣን በመሆኑ ነው ።

"በተሰሩና ውጤት በሚሰጥ አኳኋን የድሮ
ውን ማለትም የቡርዧውን የቢሮክራሲና
የህግ አፈፃፀምን መሳሪያ (አፓራተስ) ለማንኮ
ታኮትና በመጨረሻም ለመደምሰስ የሚች
ለው የሶቭየት የመንግስት ድርጅት በመሆኑ
ነው ። (ቅጽ ፳፬ ፡ ገጽ ፲፬ ይመልከቱ ።)

የሰራተኞችንና የተጨቆኑትን ብዙሀን ድርጅቶች
ወደ መንግስት አስተዳደር ተሳትፎ ውስጥ በየጊዜው
ያለምንም ማደናቀፊያና ቁጥጥር በመሳብ ለመንግስት
ቀስ በቀስ መንምኖ መጥፋት የሚያስፈልገውን መሰረት
ለመጣል በመቻሉ ነው ። ለወደፊቱም መንግስት አልባ
የኮሚኒስት ህብረተሰብ መመሥረቻ መሰረታዊ ነገሮች
አንዱ ይህ ነው ።

በዚህ ሁናቴ የሶቭየቶች ሪፑብሊክ ለረዥም ጊዜ
ሲፈለግ የነበረና አሁን የተገኘ የወዝአደሩ የኢኮኖሚ
ነፃነት ፡ የሶሻሊዝም ፍጹም ድል በውስጡ የሚፈፀም
በት መዋቅር የፓለቲካ ቅርጽ ነው ።

የፓሪሱ ኮሚውን የዚህ ቅርፅ ፅንስ ነበር ። የሶቭ
የት ስልጣን የእሱ እድገትና ተፍፃሚት ነው ።

ለዚህ ነው ሌኒን እንዲህ ያለው ።

"የሰራተኞች ፣ የወታደሮችና የገበሬዎች
ሶቭየቶች ተወካዮች ሪፑብሊክ የከፍተኛ አይ
ነት ዲሞክራታዊ ተቋም ቅርፅ ብቻ አይደ
ለም ።. . .ስቃይ የሌለው ወደ ሶሻሊዝም
መሸጋገሪያ ዋስትና ሊሰጥ የሚችል ብቸኛ[12]
መንገድም ነው ።" (ቅፅ ፳፪ ፡ ገጽ ፩፻፴፩
ይመልከቱ ።)



## ፫. የገበሬው ጥያቄ

ከዚህ ዋና ሃሳብ አራት አርእስቶች እወስዳለሁ ።

ሀ. የጥያቄው አቀራረብ ፤
ለ. ገበሬው በቡርዧ ዲሞክራቲክ አብዮት ጊዜ ፤
ሐ. ገበሬው በወዝአደሩ አብዮት ጊዜ ፤
መ. ገበሬው የሶቭየቶች ሥልጣን ከተጠናከረ
በኋላ ፤

፩. የጥያቄው አቀራረብ ፤ አንዳንድ ሰዎች በሌኒን
ትምህርቶች ውስጥ መሠረታዊ ነጥብ የገበሬው
ጥያቄ ነው ፤ ሌኒንዝም የሚነሳበት ነጥብ የገበሬው
ጥያቄ ፤ የገበሬው ሚናና ለገበሬው የሚሰጠው አንፃራዊ
ግምት ነው ብለው ያስባሉ ። ይህ ሙሉ በሙሉ ስህ
ተት ነው ። የሌኒንዝም መሠረታዊው ጥያቄና መነሻው ፤
የገበሬ ጥያቄ ሳይሆን የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ጥያቄ፤
በምን ሁኔታዎች ስር ሊገኝ እንደሚቻልና በምን
ሁኔታዎች ስር እንደሚጠናከር ነው ። ለሥልጣን በሚ
ያደርገው የመደብ ትግል እንደወዝአደሩ አጋር አድርጎ
የሚወስደው የገበሬው ጥያቄ ከዚያ የሚመነጭ ወይ
ንም ተከትሎ የሚመጣ ጥያቄ ነው ።

ይሁን እንጂ ይህ ሁናቴ የገበሬው ጥያቄ ለወዝ
አደሩ አብዮት ያለውን እጅግ ከፍተኛ የሆነ ጥቅምና
ቦታ በምንም አይነት አያሳጣውም ። ስለገበሬው ጥያቄ
በሩሲያ ማርክሲስቶች መሀከል እውነተኛ የሆነ ጥናት
የተጀመረው ልክ በመጀመሪያው አብዮት (፲፱፻፭)
ዋዜማ የዛር አገዛዝን የመገልበጡ ጥያቄና የወዝአደ
ሩን መሪነት (ሄጅመኒ) የማረጋገጡ አዳጋች ተግባር
ፓርቲውን በገጠመበት ጊዜና እየተቃረበ በመምጣት
ላይ በነበረው በቡርዧ አብዮት የወዝአደሩ አጋር ጥያቄ

እጅግ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው ጥያቄ በሆነበት ጊዜ ነበር ። በሩሲያ ውስጥ የገበሬው የበለጠ አጣዳፊ ባህርይ ያገኘው ግን በወዝአደሩ አብዮት ጊዜ እንደነበረ የታወቀ ነው ። ይህም የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ጥያቄ ፤ የበላይ ገዥነቱን የማግኘቱና ይዞ የማቆየቱ ተግባር እየተቃረበ በመምጣት ላይ በነበረበት ጊዜና የወዝአደሩ አጋር ማን እንደሚሆን ጥያቄ እንዲነሳ ባስከተለበት ጊዜ ነበር ። ይህም ደግሞ መሆን የሚገባው ነበር ። ወደ ስልጣን የሚያመሩና ስልጣን ለመያዝ የሚዘጋጁ ሁሉ እውነተኛ አጋሮቻቸው እነማን በመሆናቸው ጥያቄ ላይ የግዴታ ማሰብ ይኖርባቸዋል ።

በዚህ ረገድ የገበሬው ጥያቄ ከአጠቃላይ የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ጥያቄ ክፍል ሲሆን እጅግ ዋናኛ ከሆኑ ከሌኒንዝም ጥያቄዎች አንዱ ነው ።

በገበሬው ጥያቄ ላይ በሁለተኛው ኢንተርናሽናል ይደረግ የነበረው የግድየለሽነትና አንዳንዴም ግልጽ የሆነ ቅዋሚ የሚገለጸው በምእራብ ውስጥ ባለው የተለየ የሁኔታዎች እድገት ብቻ አይደለም ። በተቀዳሚ ሊገለጽ የሚቻለው እነዚህ ፓርቲዎች በወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ካለማመናቸው ሀቅ ፤ አብዮቱን ከመፍራታቸውና ወዝአደሩን ወደ ስልጣን ለመምራት ምንም ፍላጎት ስላልነበራቸውም ነው ። አብዮቱን የሚፈሩ ፤ ወዝአደሮችን ወደ ስልጣን ለመምራት የማያቅዱ ፤ በአብዮቱ ውስጥ ስለወዝአደሩ አጋሮች ጥያቄ ሊጨነቁ አይችሉም ። ለእነሱ የአጋሮች ጥያቄ በግድየለሽነት የሚታይ ፤ ለቅርብ ተግባርም ምንም ግምት የማይሰጠው ጉዳይ ነው ። በገበሬው ጥያቄ ላይ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ጀግኖች የሚያሳዩትን ፌዝ ፤ እንደ የጥሩ ጠባይ ምልክት ፤ እንደ "እውነተኛ" ማርክሲዝም ምልክት



ይቆጥሩታል ። እንደ እውነቱ ከሆነ ግን በዚህ ውስጥ ትንጣት ያህል ማርክሲዝም የለም ። ምክንያቱም በወዝአደሩ አብዮት ዋዜማ የገበሬውን ጥያቄ በመሰለ ታላቅ ነገር ላይ ግድየለሽነትን ማሳየት የወዝአደሩን የበላይ ገዥነት ያለመቀበል ግልባጭ ነው ። ምንም ጥርጥር የማይኖርበት ማርክሲዝምን የመካድ ምልክት ነው ።

ጥያቄው እንደሚከተለው ነው ። ከአንዳንድ የኑሮዎቹ ሁኔታዎች የተነሳ በገበሬው ውስጥ ያሉትና ገና ያልተገለጡት አብዮታዊ ችሎታዎች የተበዘበዘውን አብዛኛውን የገበሬ ክፍል ካሁን በፊት በምእራቡ የቡርዧ አብዮቶች ጊዜ ደጋፊ (ደጀን) ከነበረበትና አሁንም ድረስ ከሆነው አላቅቆ ወደ ወዝአደሩ ደጋፊነት ወደ ወዝአደሩ አጋርነት የመለወጥና ለወዝአደሩ አብዮት የመጠቀም <u>አንዳች ተስፋ ፤ አንዳች መሠረት</u> አለ?

ለዚህ ጥያቄ ሌኒኒዝም በአወንታ ይመልሳል ። ማለትም እነዚህ አብዮታዊ ችሎታዎች በአብዛኛው ገበሬ መሀከል መኖራቸውንና እነዚህንም ለወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ጥቅሞች ለማዋል እንደሚቻል ያምናል ።

የሶስቱ የሩሲያ አብዮቶች ታሪክ በዚህ ጉዳይ ላይ የሌኒንዝምን ማጠቃለያዎች ሙሉ በሙሉ ትክክለኛነት በጥሩ መረጃ አረጋግጦአል ።

ስለሆነም ለፍቶ አዳሪው ሰፊው ገበሬ ከባርነት ፤ ከብዝበዛ ፤ ከጭቆናና ከድህነት ለመላቀቅ በሚያደርገው ትግል መደገፍ አለበት የሚል ተግባራዊ የሆነ ማጠቃለያ ይከተላል ። ይህ ማለት ደግሞ ወዝአደሩ ማንኛውንም የገበሬ እንቅስቃሴ ይደግፋል ማለት አይደለም ። እዚህ ላይ ለማለት የፈለግነው በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ ለወዝአደሩ የአርነት እንቅስቃሴ ሁኔታውን አመቺ

ለሚያደርግ ፣ ወደወዝአደሩ አብዮት በዚህም ሆነ በዚያ መንገድ ጠቃሚ የሚሆኑ ነገሮችን ለሚያመጣ ፣ ገበሬውን ወደ ሠራተኛው መደብ አጋርና ደጀንነት (ደጋፊነት) ለመለወጥ ለሚረዳ የገበሬው እንቅስቃሴ ወይንም ትግል ስለሚሰጠው ድጋፍ ነው ።

፪. <u>ገበሬው በቡርዧ ዲሞክራሲያዊ አብዮት ጊዜ</u> ፣ ይህ ጊዜ ከመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት ጀምሮ (፲፱፻፭) እስከ ሁለተኛው አብዮት (፲፱፻፲፯) ድረስ ሁለቱንም የጊዜ ክልሎች ይዞ ያለው ነው ። የዚህ ጊዜ ባህርይው የገበሬው ከሊበራል (ለዘብተኛ) ቡርዧ ተጽእኖ መላቀቅ ፣ የገበሬው ከካዴቶች[13] በገፍ እየለቀቀ መውጣትና ወደ ወዝአደሩ ፣ ወደቦልሼቪኮች ፓርቲ ወገን መለወጥ ነው ። የዚህ ጊዜ ታሪክ ገበሬውን ለማሸነፍ ሲባል በካዴቶችና (በለዘብተኛ ቡርዧው) በቦልሼቪኮች (በወዝአደሩ) መሀከል የነበረ የትግል ታሪክ ነው ። የዚህ ትግል ውጤትም በዱማው[14] ጊዜ ለየለት ። ምክንያቱም አራቱም የዱማ ጊዜዎች ለገበሬው ተጨባጭ ትምህርት በመሆን ረድተውታል ። ይህ የቀሰሙት ትምህርት ገበሬዎቹን ያሳወቃቸው ሀቅ ከካዴቶች እጅ መሬትም ይሁን ነፃነት እንደማያገኙ ፣ ዛሩ ሙሉ በሙሉ የመሬት ከበርቴዎችን እንደሚደግፍ ፣ ካዴቶች ዛሩን እንደሚደግፉ ፣ ገበሬዎች ለድጋፍ ሊተማመኑበት የሚችሉት አንድ ሀይል ብቻ እንደሆነና እሱም የከተማ ሠራተኞች የወዝአደሮች ሀይል እንደሆነ ነው ። የኢምፔሪያሊስቶች ጦርነትም ገበሬዎች በዱማ ጊዜ የቀሰሙት ትምህርት ትክክል መሆኑን ይበልጥ አረጋገጠላቸው ። ይህም የገበሬዎቹን ከቡርዧው ሙሉ በሙሉ እየለቀቁ መውጣትን ሲያስከትል የሊበራል (የለዘብተኛ) ቡርዧውንም ብቸኛ ሆኖ መቅረት እንዲሁ የተሟላ ያደርገ



ዋል (አደረገው) ። ምክንያቱም በጦርነት ጊዜ የነበሩት ዓመታት ከዛሩና አጋሮቹ ከሆኑት ቡርዧዎች ሰላም የማግኘቱ ተስፋ ከንቱ ድካምና ፍጹም አታላይ መሆኑን ገለጠላቸው ። ካለዱማው ጊዜ ተጨባጭ ትምህርት ፣ የወዝአደሩ መሪነት ፍጹም የማይቻል ይሆን ነበር ።

በቡርዧ ዲሞክራቲክ አብዮት የሰራተኛውና የገበሬው አጋርነት መልክ የያዘው እንዲህ ነበር ። የዛር አገዛዝን ለመጣል በተደረገው የወዝአደሩና የገበሬው የጋራ ትግል የወዝአደሩ መሪነት—ወደ የካቲት ፲፱፻፲፯ አብዮት የመራው የወዝአደሩ መሪነት የተገኘው እንዲህ ነበር ።

እንደሚታወቀው በምእራብ የተካሄደው የቡርዧ አብዮት (በብሪታንያ ፣ ፈረንሳይ ፣ ጀርመን ፣ አውስትሪያ) የተለየ መንገድ ወስዶአል ። እዚያ በአብዮቱ ውስጥ የመሪነቱን ቦታ የያዘው ለዘብተኛ (ሊብራል) ቡርዧው እንጂ ከደካማነቱ የተነሳ ነፃ የሆነ የፖለቲካ ሀይል ያልወከለውና ሊወክልም ያልቻለው ወዝአደሩ አልነበረም ። እዚያ ገበሬው ከገባርነት ስርአት ወጥቶ ነፃነቱን ያገኘው ከቡርዧው እጅ እንጂ በቁጥር ደካማና እንዲሁም ያልተደራጀ ከነበረው ከወዝአደሩ አልነበረም ። እዚያ ገበሬው ከለዘብተኛ (በሊብራል) ቡርዧው ጋር ጎን ለጎን ተሰልፎ ነው በአሮጌው ስርአት ላይ የተነሳው ፣ እዚያ ገበሬው የቡርዧው ደጋፊ (ደጀን) ሆኖ ነው የተሰለፈው ። ከዚህም የተነሳ እዚያ አብዮቱ ለቡርዧው ትልቅ የፖለቲካ ተሰሚነትና እጅግ ከፍተኛ ሀይል ሰጥቶታል ።

ሩሲያ ውስጥ በተቃራኒ የቡርዧው አብዮት ፍጹም የተለየ ውጤት አስገኝቷል ። በሩሲያ ውስጥ የተ

ካሄደው አብዮት ያመራው ቡርዧው እንደ አንድ የፖለቲካ ሀይል እንዲዳከም እንጂ እንዲጠናከር አልነበረም ። አብዮቱ ያመራው የቡርዧው የፖለቲካ አልነበዎች እንዲጨምር ሳይሆን ዋና ደጋፊው የነበረውን ገበሬ እንዲያጣ ወደማድረጉ ነበር ። በሩሲያ ውስጥ የተካሄደው የቡርዧ አብዮት በአብዮታዊው ወዝአደር አካባቢ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ገበሬዎችን በማሰለፍ ወዝአደሩን ግንባር ቀደም አደረገው እንጂ ሊበራል ቡርዧውን አይደለም ።

በነገራችን ላይ ፣ በሩሲያ ውስጥ የተካሄደው የቡርዧ አብዮት ከሌላው ሲወዳደር እንደዚያ ባለች አጭር ጊዜ ውስጥ ወደ ወዝአደሩ አብዮት ለምን እንደተሳለፈ ከላይ የተጠቀሰው ያስረዳል ። የወዝአደሩ መሪነት ለወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ፅንስና መሸጋገሪያ ደረጃው ነበር ።

ይህም በምእራብ ቡርዧ አብዮት ታሪክ ውስጥ አምሳያ የሌለው የሩሲያ አብዮት ልዩ ክስተት (ፌኖሚና) እንዴት ሊገለጽ ይቻላል? ይህ ልዩ ሁኔታ ከየት መጣ?

ይህ ሊገለጽ የሚቻለው በሚከተሉት ሀቆች ነው ። ቡርዧ አብዮት በሩሲያ ውስጥ የተካሄደው ከምእራብ የበለጠ የዳበረ የመደብ ትግል ባለበት ሁኔታ ስር ነበር ። ገና በዚያን ጊዜ እንኳ የሩሲያ ወዝአደር ነፃ የፖለቲካ ሀይል ሆኖ ነበር ። ሊበራል ቡርዧው ግን በወዝአደሩ አብዮታዊ መንፈስ ተደናግጦ የአብዮታዊ መንፈስ መልኩን እርግፍ አድርጎ ጥሎ (በተለይ ከ፲፱፻፭ ትምህርት በኋላ) ከዛሩና ከመሬት ከበርቴዎች ጋር በመተባበር በአብዮቱ ላይ ፣ በሰራተኞችና በገበሬዎች ላይ ፊቱን አዞረ ።



የሩሲያውን ቡርዧ አብዮት ልዩ ባህርይ የሚወስኑትን ሁኔታዎች ለማመን የሚከተሉትን ልብ ማለት ይኖርብናል ።

ሀ. በአብዮቱ ዋዜማ የሩሲያ ኢንዱስትሪዎች አምሳያ የሌለው ክምችት ፣ ለምሳሌ በሩሲያ ውስጥ ከነበሩት ጠቅላላ ሰራተኞች መሀል ፶፬ በመቶ የሚሆኑት የተቀጠሩት እያንዳንዳቸው ከ፭፻ ሰራተኛ በላይ በሚቀጥሩ ድርጅቶች ውስጥ እንደሆነ የታወቀ ነው ። ነገር ግን እንደዚያ በጣም በዳበረችው በሰሜን አሜሪካ እንደዚህ ባሉ ድርጅቶች (ኢንተርፕራይዚስ) ውስጥ የሚቀጠሩት ፣ ካሉት ጠቅላላ ሰራተኞች መሀል ፴፫ ከመቶ አይበልጡም ነበር ። ቦልሼቪኮችን ከመሰለ አብዮታዊ ፓርቲ መኖር አንፃር ሲታይ ደግሞ ይህ በሩሲያ ውስጥ የነበረው ሁኔታ የሩሲያን የሰራተኛ መደብ ወደ ታላቅ አብዮታዊ ኃይል ማሸጋገሩና በአገሪቱም የፖለቲካ ሕይወት ውስጥ ከፍተኛ ተሳትፎ እንዲያደርግ መገፋፋቱ እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ።

ለ. በፋብሪካዎች ውስጥ ያለው እጅግ አስከፊ የሆነ ብዝበዛ ከመጠን በላይ ከሆነው ከዛሩ ደጋፊዎች የፖሊስ አገዛዝ ጋር መጣመር ፣ ይህም ሁናቴ ማንኛውንም የሰራተኛውን ከፍተኛ የስራ ማቆም አድማ ወደ አስደናቂ የፖለቲካ ድርጊት ይለውጥ ነበር ። ይህም የሰራተኛውን መደብ ሙሉ በሙሉ አብዮታዊ ሀይል ወደመሆን አጠናከረው ።

ሐ. ከ፲፱፻፭ አብዮት በኋላ የዛር አገዛዝን ወደ መለማመጡ የተለወጠውና ግልፅ ፀረ አብዮታዊ

የሆነው የሩሲያ ቡርዧ የፖለቲካ ልፍስፍስነት ፤ ይህም ሀቅ የሚገለጸው የሩሲያ ቡርዧ በዛሪዝም ጉያ ውስጥ ሮጦ እንዲገባ በአሽቀንጠረው በሩሲያ ወዝአደር የአብዮታዊነት መንፈስ ብቻ ሳይሆን ቡርዧው ራሱ ከአገዛዙ ጋር በገባው ውል ውስጥ ባለው ቀጥተኛ ጥቅምም ጭምር ነው ።

መ. በገጠሩ ውስጥ እጅግ አስከፊና የማይታገሱት የሆነ የገባርነት ርዝራዥ ከመሬት ከበርቴዎች ገደብ የሌለው ሀይል ጋር መጣመር ፤ ይህም ገበሬውን ወደአብዮቱ እንቀልባ የወረወረው ሁኔታ ነው ።

ሠ. ማንኛውንም በህይወት ያለ ነገርን የሚያፍነውና በቆራጭ ፈላጭነቱ አማካይነት የካፒታሊስቶችንና የመሬት ከበርቴዎችን ጭቆና የሚያባብሰው የዛር አገዛዝ ፤ ይህም የሰራተኞችንና የገበሬዎችን ትግል በአንድ አብዮታዊ ማእበል ውስጥ አጣመረው ።

ረ. እነዚህን በሩሲያ የፖለቲካ ኑሮ ውስጥ ያሉትን ቅራኔዎች በሞላ ወደ ከፍተኛ አብዮታዊ ቀውስ ያደባለቃቸውና ለአብዮቱ ታላቅ የግፊት ሀይል የሰጠው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት ነው ።

በእነዚህ ሁኔታዎች ስር ገበሬዎች ወደማን ዞረው ርዳታን ይሻሉ? በመሬት ከበርቴዎች ገደብ የሌለው ሀያልነት ላይ ፣ በዛሩ ቆራጭ ፈላጭነት ላይና ወደ ውድቀት እየመራቸው ባለው አጥፊው ጦርነት ላይ ባላቸው ቅዋሚ ከማን ዘንድ ድጋፍ ሊፈልጉ ይችላሉ? ከሊበራል ቡርዧው ነው? ግን ታዲያ የአራቱም የዱማ ጊዜዎች ረዥም ልምድ እንዳረጋገጠው ሊበራል ቡርዧዋው ጠላት ነበር ። ከሶሻሊስት "አብዮተኞችስ"፤ ሶሻሊ-



ስት "አብዮተኞች" እርግጥ ከካዴቶች "የተሻሉ" ነበሩ ። ፕሮግራማቸውም "ምቹ የሆነ" የገበሬ ፕሮግራም ለመሆን ምንም ያህል የማይቀረው ነበር ። ግን ታዲያ ሶሻሊስት "አብዮተኞች" በገበሬዎች ላይ ብቻ ለመተማመን ማሰባቸውንና ጠላት በተቀዳሚ ሀይሉን በሚሰበስብበት በከተማ ውስጥ ደካማ መሆናቸውን ስንመለከት ምን ሊያደርጉላቸው ይችላሉ? በገጠርም ይሁን በከተማ ፣ በሙሉ ልብ ፣ በግንባር ቀደምትነት በመሰለፍ ዛሩንና የመሬት ከበርቴዎችን ሊወጋ የሚችል ፣ ገበሬዎች ከባርነት ፣ ከመሬት እጦት ፣ ከጭቆናና ከጦርነት ራሳቸውን እንዲያላቅቁ የሚረዳቸውና ምንም ከማድረግ የማይመለስ አዲስ ሀይል ታዲያ የት ነበር? ለመሆኑ እንዲህ ያለው ሀይል በሩሲያ ነበር? አዎን ነበር ። እሱም ገና ያኔ በ፲፱፻፭ ጥንካሬውን ፣ እስከመጨረሻው ድረስ ለመዋጋት ያለውን ችሎታ ፣ ቆራጥነቱንና አብዮታዊ መንፈሱን ያሳየው የሩሲያ ወዝአደር ነበር ።

ያም ሆነ ይህ እንዲህ አይነት ሌላ ሀይል አልነበረም ፣ የትም ደግሞ ሊገኝ አይችልም ነበር ።

ለዚህ ነው ገበሬው ፊቱን በካዴቶች ላይ አዙሮ ራሱን ከሶሻሊስት "አብዮተኞች" ጋር እንዳጣመረ ወዲያውኑ እንደ ሩሲያ ወዝአደር ላለ ቆራጥ የአብዮቱ መሪ የመሪነቱን ቦታ የመልቀቁን አስፈላጊነት የተረዳው ።

የሩሲያን ቡርዧ አብዮት የተለየ ባህርይ የወሰኑት ሁኔታዎች እንዲህ ነበሩ ።

፩. ገበሬው በወዝአደሩ አብዮት ጊዜ ፤ ይህ ጊዜ ከየካቲት ፲፱፻፲፯ አብዮት እስከ ጥቅምት ፲፱፻፲፯ አብዮት ድረስ ያለው ጊዜ ነው ። ይህ ጊዜ ከሌላው ሲወ

ዳደር አጭር ነው ። በጠቅላላው ስምንት ወራት ነበሩ።
ነገር ግን ከፖለቲካ ብልፅግናና ሰፊው ህዝብ በአብዮ
ታዊ ትምህርት ከመሰልጠኑ አንፃር ሲታዩ እነዚህ
ስምንት ወራት ከብዙ አመታት ተራ የሆነ ህገ መንግስ
ታዊ እድገት ጋር እኩል ሊቀመጡ ይችላሉ ። ምክንያ
ቱም ስምንት የአብዮት ወራት ነበሩና ነው ። የዚህ ጊዜ
መለያ ባህርይው የገበሬው አብዮታዊነት በይበልጥ
መጨመር፤ ከሶሻሊስት "አብዮተኞች" ሀሰተኛና የተሳሳተ
እምነት መላቀቅ ፣ የገበሬዎች ከሶሻሊስት "አብዮተ
ኞች" በገፍ እየለቀቁ መውጣት ፣ ሀገሪቱን ወደ ሰላም
ለመምራት ወደሚችለውና ቁርጠኛ አብዮታዊ ሀይል
ወደሆነው ወደ ወዝአደሩ መዞርና በእሱም አካባቢ በቀ
ጥታ መሰለፍ ነው ። የዚህ ጊዜ ታሪክ ብዙሀኑን ገበሬ
ዎች ወደራሳቸው ወገን ለማድረግ በሶሻሊስት "አብ
ዮተኞችና" (የንኡስ ከበርቴ ዲሞክራሲ) በቦልሼቪኮች
(የወዝአደሩ ዲሞክራሲ) መሀከል የተደረገ ትግል ታሪክ
ነበር ። የዚህ ትግል ውጤት በገሀድ የታየው በጥምሩ
መንግስት ጊዜ ፣ በክሬንስኪ[15] ጊዜ ፣ ማለትም ሶሻሊስት
"አብዮተኞችና" ሜንሼቪኮች የመሬት ከበርቴዎችን
መሬት መውረስ አሻፈረን ባሉበት ጊዜ ፣ ሜንሼቪኮችና
"ሶሻሊስት አብዮተኞች" ጦርነቱ እንዲቀጥል ትግል
ባደረጉበት ጊዜ ፤ በግንባሩ በተካሄደው የሰኔው የማጥ
ቃት እርምጃ ጊዜ ፣ ወታደሮች ሲያጠፉ በሞት እንዲቀጡ
በተወሰነበት ጊዜና በኮርኒሎቭ ማመጽ ጊዜ ነበር ።

በፊት ማለትም ቀደም ብሎ በነበረው ጊዜ መሰረ
ታዊው የአብዮቱ ጥያቄ የዛሩንና የመሬት ከበርቴዎችን
ስልጣን መገልበጥ ሲሆን አሁን ከየካቲት አብዮት
በኋላ ባለው ጊዜ ፣ ዛሩ ካሁን ወዲያ በሌለበት ጊዜ ፣
ማለቂያ የሌለው ጦርነት የሀገሪቱን ኢኮኖሚ ባራቆተበ



ትና ገበሬውን ፍጹም ውድቀት ውስጥ በከተተበት ጊዜ
ጦርነቱን ማጥፋት የአብዮቱ ዋና ጥያቄ ሆነ ። የጥያቄ
ዎች ማእከላዊ ነጥብ ሙሉ በሙሉ ውስጣዊ ከሆኑ
ጥያቄዎች ወደ ዋናው የጊዜው ጥያቄ ማለትም ወደ
ጦርነቱ በግልጽ ዞረ ። "ጦርነቱን አብቁት" ፣ "ከጦር
ነቱ እንውጣ" ፤ እንዲህ ነበር በጦርነቱ የተሰላቸው
ሀገር ፣ በተለይም የገበሬው ጠቅላላ ጩኸት ።

ይሁን እንጂ ከጦርነቱ ለመውጣት ጊዜያዊውን
መንግስት መገልበጥ ፣ የቡርዧውን ስልጣን መገልበጥ ፣
የሶሻሊስት አብዮተኞችንና የሜንሼቪኮችን ስልጣን መገ
ልበጥ ፣ አስፈላጊ ነበር ። ምክንያቱም እነሱ ብቻ ነበሩ
ጦርነቱን ወደ "ድል ፍጻሜ" በመጎተት ላይ የነበሩት።
ቡርዧውን ከመገልበጥ በስተቀር ሌላ ተግባራዊ የሆነ
ከጦርነቱ መውጫ መንገድ አልነበረም ።

ይህ አዲስ አብዮት የወዝአደሩ አብዮት ነበር ።
ምክንያቱም የኢምፔሪያሊስት ቡርዧውን የመጨረሻ
ቡድን ፣ አክራሪ የግራ ክንፉን የሶሻሊስት አብዮተኞችን
ፓርቲና ሜንሼቪኮችን ከስልጣን አስወገዳቸው ። ይህንን
ያደረገው አዲስ ወዝአደራዊ ስልጣን ፣ የሶቭየቶች ስል
ጣን ለማቋቋም ፣ በኢምፔሪያሊስት ጦርነት ላይ ትግል
የሚያካሂደውንና ለዲሞክራሲያዊ ሰላም የአብዮታዊ
ትግል ፓርቲ የሆነውን የቦልሼቪኮች ፓርቲ ፣ የአብዮ
ታዊ ወዝአደሩን ፓርቲ ስልጣን ላይ ለማውጣት ነበር ።
ሰራተኞች ለሰላም ፣ ለሶቭየቶች ስልጣን የሚያደርጉትን
ትግል አብዛኞዎቹ ገበሬዎች ይደግፉ ነበር ።

ለገበሬው ሌላ አማራጭ መንገድ አልነበረም ።
ሌላ አማራጭ መንገድ ሊኖርም አይችልም ።

በዚህ መንገድ ስናየው የክሬንስኪ ጊዜ ሰፊው
ለፍቶ አዳሪ ገበሬ ተጨባጭ የሆነ ታላቅ ትምህርት

ያገኘበት ጊዜ ነበር ። ምክንያቱም ሶሻሊስት አብዮተ
ኞችን ሜንሼቪኮች በስልጣን ላይ እስከሆኑ ድረስ ሀገ
ራቱ ራስዋን ከጦርነቱ እንደማታላቅቅና ገበሬዎች
መሬትም ሆነ ነፃነት ፍጹም እንደማያገኙ ሜንሼቪኮችና
ሶሻሊስት አብዮተኞች ከካዴቶች የሚለዩት ባማረ ንግ
ግራቸውና የውሸት ተስፋቸው እንጂ በተረፈ ግን ያው
የድሮው አይነት ኢምፔሪያሊስት የሆነ የካዴት መመሪያ
እንደሚከተሉ ፣ ሀገራቱን በቀጥተኛ መንገድ ሊመራት
የሚችለው ሀይል የሶቭየቶች ሀይል ብቻ መሆኑን ደህና
አድርጎ ሊያሳያቸው በመቻሉ ነው ። የጦርነቱ ይበልጥ
እየተራዘመ መሄድ ያረጋገጠው ይህንን ሀቅ ሲሆን
አብዮቱን በማፋፋም በሚሊዮን የሚቆጠሩ ገበሬዎችና
ወታደሮች በወዝአደሩ አብዮት አካባቢ በቀጥታ እንዲ
ሰለፉ ገፋፍቶአቸዋል ። የሶሻሊስት አብዮተኞችና የሜን
ሼቪኮች ብቸኛ ሆኖ መቅረት የማያወዛግብ ሀቅ ሆነ ።
ካለዚያ የጥምር ጊዜ ተጨባጭ ትምህርት የወዝአደሩ
የበላይ ገዥነት ፍጹም የማይቻል ይሆን ነበር ።

የቡርዧ አብዮት ሂደት ወደ ወዝአደሩ አብዮት
እንዲተላለፍ አመቺና የቀለለ ያደረጉት ሁኔታዎች እን
ዲህ ነበሩ ።

የወዝአደሩ የበላይገዥነት በሩሲያ ውስጥ መልክ
የያዘውም በዚህ ሁናቴው ነበር ።

፬. ገበሬው ከሶቭየት ስልጣን መጠናከር በኋላ ፣
የአብዮቱ የመጀመሪያው ጊዜ ዋና ዓላማ የዛሩን አገዛዝ
መገልበጥ ሲሆንና ከዚያም ከየካቲት አብዮት በኋላ
ተቀዳሚው ዓላማ ቡርዧውን ገልብጦ ከኢምፔሪያሊስት
ጦርነት መውጣት ሲሆን አሁን ከእርስ በርስ ጦርነት
መደምሰስና ከሶቭየት ስልጣን መጠናከር በኋላ ኢኮ



ኖሚ የመገንባት ጥያቄዎች ወደ ግንባር ቀደምትነት
መጡ ። የተወረሱትን እንዱስትሪዎች ማጠናከርና ማዳ
በር ፣ ለዚህም ጉዳይ በመንግስት ቁጥጥር ስር በሚካሄድ
ንግድ አማካይነት እንዱስትሪን ከገበሬ ኢኮኖሚ ጋር
ማያያዝ ፣ ትርፍ ምርት የመውሰድን ስርአት በገንዘብ
ሳይሆን በአይነት ታክስ መተካት ፣ ሲሆን ይህም የሚደ
ረገው ቀስ በቀስ በአይነት የሚደረገውን ታክስ ዝቅ
እያደረጉ በኋላ የኢንዱስትሪን ምርት ከገበሬ እርሻ
ምርት የመለዋወጥ ስርአት ላይ ለመድረስ ነው ። ሰፊ
ውን ገበሬ ወደዚህ በመሳብ ንግድ እንዲንሰራራ ማድ
ረግና የህብረት ስራ ድርጅትን ማሳደግ ። የሶሻሊስት
ኢኮኖሚን መሠረት በመጣል ጎዳና ላይ ኢኮኖሚን
በመገንባት በኩል ሊወስዱ ስለሚገባቸው አጣዳፊ
ተግባሮች ሌኒን ያወጣው ንድፍ እንዲህ ነው ።

ይህ ተግባር እንደ ሩሲያ ላለች የገበሬ ሀገር ከአ
ቅም በላይ ሳይሆን አይቀርም ተብሏል ። እንዲያውም
አንዳንድ ተጠራጣሪዎች ተምኔታዊ ነው ፣ የሚሆን
ነገር አይደለም ይላሉ ። ለምን ቢሉ ገበሬ ገበሬ ነው ፣
ትናንሽ አምራቾችን ይይዛል ፣ ስለሆነም የሶሻሊስትን
የምርት መሠረት በማደራጀት በኩል ምንም ጥቅም
ሊሰጥ አይችልም ይላሉ ።

ነገር ግን ተጠራጣሪዎቹ ተሳስተዋል ፣ ምክንያቱም
በአሁኑ ጊዜ ትልቅና ወሳኝ የሆነ ግምት ያላቸውን
አንዳንድ ሁኔታዎች ልብ ሳይሉ ቀርተዋል ። እስቲ
ከእነዚህ ውስጥ ከፍተኞቹን እንይ ።

መጀመሪያ ፣ በሶቭየት ህብረት ውስጥ ያለ ገበሬ
በምእራብ ውስጥ ካለ ገበሬ ጋር መምታታት የለበትም።
በሶስት አብዮቶች ውስጥ ትምህርት የቀሰመ ገበሬ ፣

ከወዝአደሩ ጋር ጎን ለጎን በመሆንና በእርሱም መሪነት ስር የዛሩንና የቡርዧውን ስልጣን የተዋጋ ገበሬ ፡ ከወዝአደሩ አብዮት እጅ መሬትና ሰላምን የተቀበለና በዚህም ምክንያት የወዝአደሩ ደጋፊ የሆነ ገበሬ ፡ እንዲህ ያለው ገበሬ በቡርዧ አብዮት ጊዜ በሊበራል ቡርዧው መሪነት ስር ከተዋጋ ገበሬ ፡ መሬት ከቡርዧው እጅ ካገኘና ከዚህም የተነሳ የቡርዧው ደጋፊ ከሆነ ገበሬ የተለየ መሆን ይኖርበታል ። ከወዝአደሩ ጋር ባለው በፖለቲካ ጓደኝነቱና በፖለቲካ ትብብሩ ፍስሐን የለመደና ነፃነቱም ከዚሁ ጓደኝነትና ትብብር በመምጣቱ ውለታ ያለበት የሶቭየት ገበሬ ከወዝአደሩ ጋር ላለው የኢኮኖሚ መረዳዳት እጅግ ምቹ የሆነ ሁኔታን ከሚፈጥር ኃይል ሌላ ሊሆን እንደማይችል ማረጋገጡ እስከዚህም አስፈላጊ አይደለም ።

ኤንግልስ "የፖለቲካ ስልጣኑ በሶሻሊስት ፓርቲው መያዝ እስከዚህም ሩቅ የማይል ጊዜ ጉዳይ ሆኗል ስለዚህም የፖለቲካ ስልጣን ለመያዝ ከተፈለገ ይህ ፓርቲ መጀመሪያ ከከተማ ወደገጠር መሄድ አለበት ፤ በገጠሩ ውስጥ ሀይል ያለው መሆን አለበት" ይላል ። (ኤንግልስ የገበሬው ጥያቄ ፣ ፲፱፻፷፪ እትም ይመልከቱ) ይህንን የጻፈው በ፲፰፻፺፬ አካባቢ ሲሆን በሃሳቡ የነበረው የምዕራቡ ገበሬ ነበር ። የሩሲያ ኮሚኒስቶች በዚህ መልክ በሶስት አብዮቶች ጊዜ እጅግ ብዙ የሆነውን ሥራ ካከናወኑ በኋላ ፣ የምእራብ ጓዶች በሀልማቸው እንኳን ሊያስቡት ከሚችሉት በላይ በገጠሩ ውስጥ ተሰሚነትና ድጋፍ ገና ከአሁኑ ለማግኘት መቻላቸውን ማረጋገጥ ያስፈልጋል? ይህ ሁኔታ በሩሲያ ሰራተኛ መደብና በገበሬው መሀከል በኢኮኖሚ መረዳዳት መደራጀትን በማያጠራጥር ሁኔታ አመቺ ሊያደርግ እንደሚችል እንዴት ለመካድ ይቻላል?



ተጠራጣሪዎቹ ፡ ትናንሽ ገበሬዎች የሶሻሊስት ሥርዓትን ከመገንባት ጋር የማይገጥሙ ናቸው ብለው ያምናሉ ። ግን እስቲ ኤንግልስ ስለምእራብ ትናንሽ ገበሬዎች የሚለውን አዳምጡ ።

"እኛ ያለጥርጥር የትንሹ ገበሬ ወገን ነን ። የወደቀበትን ኑሮ የተሻለ ለማድረግ ፣ ወደህብረት ስራ ድርጅት ለማለፍ ከፈለገ ወደዚያ መሸጋገር ምቹ እንዲሆንለት ፣ በዚህ ነገር ላይ ለመወሰን ካልቻለ ስለነገሩ አውጥቶ ለማውረድ እንዲችል በራሱ ትንሽ መሬት ላይ እንኳን ረዘም ላለ ጊዜ ለመቆየት ከፈለገ እንዲቆይ ማንኛውንም ሊሆን የሚገባውን ነገር ሁሉ እናደርጋለን ። ይህንንም የምናደርገው የራሱን ስራ የሚሰራው ትንሹ ገበሬ ወደኛ ወገን ሊመጣ ይችላል ብለን ስለምናስብ ብቻ ሳይሆን ለፓርቲውም ቀጥተኛ ጥቅም ስንል ነው ። ገና ገበሬ ሆነው እያሉ ወደ እኛ ወገን ልንወስዳቸው ከምንችለው ውስጥ ወደ ወዝአደሩ ውስጥ ከመወርወር ለማዳን በቻልነው መጠን ህብረተሰባዊ ሽግግሩም (ሶሻል ትራንስፎርሜሽን) በዚያ መጠን በቀለለና በተፋጠነ አኳኋን ይከናወናል ። ይህንንም ሽግግር ካፒታሊስት አመራረት እስከ መጨረሻ ውጤቱ በየቦታው እስኪያድግ ድረስ ፣ የመጨረሻው ትንሹ እደጠበብተኛና የመጨረሻው ትንሹ ገበሬ በካፒታሊስት ከፍተኛ ደረጃ አመራረት ስር እስኪወድቅ ድረስ መዘግየቱ ለኛ ዋጋ ቢስ ይሆናል ። በዚህ ጉዳይ ለገበሬው ጥቅም ሲባል

መስዋእት የሚደረግና ከህዝቡ ገንዘብ (ፓብ
ሊክ ፋንድ) ውስጥ የሚከፈል ቁስአካላዊ
ነገር ከካፒታሊስት ኢኮኖሚ አንፃር ሲታይ
እንዲሁ እንደ ተጣለ ገንዘብ ሊቆጠር ይችል
ይሆናል ። ይሁን እንጂ እጅግ ጥሩ መዋእለ
ንዋይ ነው ። ምክንያቱም በአጠቃላይ የህብረ
ተሰብ እንደገና አደረጃጀት ወጪ ላይ ምናል
ባት አስር እጥፉን ያድናልና ነው ። ስለዚህ
በዚህ መንፈስ በገበሬው በኩል በጣም ቻይ
ልንሆን እንችላለን ።" (ኤንግልስ ፡ የገበ
ሬው ጥያቄ ፡ ፲፱፻፷፪ እትም ይመልከቱ ።)

የምእራብ ገበሬዎችን በሃሳቡ ይዞ ኤንግልስ
ያለው ይህ ከላይ የጠቀስነው ነው ። ግን ታዲያ ኤን
ግልስ ያለው ከየትም ይልቅ በጣም በቀላልና በተሟላ
አኳኋን የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ባለበት አገር ሊከና
ወን እንደሚችል ግልጽ አይደለም?

"የራሱን ስራ የሚሰራ ትንሽ ገበሬ" ወደ እኛ
ወገን ሊመጣና ለዚህም የሚደረጉ "ቁስአካላዊ መስ
ዋእቶችና" "ለገበሬው ሊደረግ" የሚያስፈልገው
"ቸርነት" ባንድ ጊዜና ሙሉ በሙሉ ሊደረግ የሚቻ
ለው በሶቭየት ሩሲያ ብቻ እንደሆነ ግልጽ አይደለም?
እነዚህና ለገበሬው ጥቅም የሚሆኑ ተመሳሳይ እርምጃ
ዎች ገና ከአሁኑ በሩሲያ ውስጥ በመካሄድ ላይ መሆና
ቸው ግልጽ አይደለም? ታዲያ ይህ ሁናቴ በተራው
በሶቭየቶች ሀገር ኢኮኖሚ የመገንባቱን ስራ የቀለለ
የሚያደርግና የሚያራምድ መሆኑ እንዴት ይካዳል?

ሁለተኛ በሩሲያ ውስጥ ያለ ግብርና በምእራብ
ካለው ጋር መምታታት የለበትም ። እዚያ ግብርና በተ



ለመደው የካፒታሊዝም መስመሮች ፡ በገበሬዎች መሀ
ከል ባለ ከፍተኛ የልዩነት ሁኔታ ስር ፡ ባንድ በኩል
በታላላቅ የመሬት ይዞታዎችና በግላዊ ካፒታሊስት
ላቲፉንዲያ ሲካሄድ በሌላ በኩል ተመጽዋችነት ፡
ድህነትና የደመወዝ ባርነት ባላበት ሁኔታ ስር እያደገ
ነው ። ከዚህም የተነሳ እዚያ መገነጣጠልና መበስበስ
ሊሆን የሚገባው ነው ። በሩሲያ ግን እንዲህ አይደለም ።
ሌላው ቢቀር የሶቭየት ስልጣን መኖርና ዋና ዋናዎቹ
የምርት መሣሪያዎችና የምርት መገልገያዎች መወረስ
እንደዚህ አይነቱን እድገት ስለሚያስወግድ በሩሲያ
ውስጥ ግብርና እንዲያ ባለ መንገድ ሊያድግ አይች
ልም ። በሩሲያ የግብርና እድገት ለየት ባለ መንገድ ፡
በሚሊዮን የሚቆጠሩ ትናንሽና መካከለኛ ገበሬዎችን
በህብረት ሥራ ማህበር በማደራጀት መንገድ ፡ በገጠር
ውስጥ መንግስት በሚያደርገው ልዩ የብድር አሰጣጥ
የሚደገፍ ሰፊ የሆነ የህብረት ስራ ድርጅት እንቅስቃሴ
በማሳደግ መንገድ እድገቱ መቀጠል አለበት ። ስለ
ህብረት ሌኒን በጻፉቸው ላይ በአገራችን ውስጥ የግብ
ርና እድገት በአዲስ መንገድ ፡ በህብረት ስራ ድርጅት
አማካይነት ፡ ብዙሀኑን ገበሬዎች ወደ ሶሻሊስት መገን
ባት በመሳብ መንገድ ፡ ቀስ በቀስ የኮሌክቲባይዜሽንን
መርህ በግብርና ውስጥ መጀመሪያ በግብይት መስክ
በኋላም በእርሻ ምርቶች አመራረት መስክ በማስገባት
መንገድ መቀጠል እንዳለበት የጠቀሰው በትክክል ነው ።

በዚህ በኩል እጅግ ከፍተኛ ግምት የሚሰጣቸው
ከእርሻ የህብረት ስራ ድርጅት ጋር በመያያዝ በገጠር
ውስጥ የሚታዩ ብዙ አዳዲስ ክስተቶች አሉ ። ወደፊት
ብዙ ተስፋ ባላቸው እንደ ቃጫ ፡ ድንች ፡ ቅቤ. . .ወዘተ.
ምርት ባሉ በልዩ ልዩ የእርሻ ክፍሎች አዳዲስ የሆኑ
ታላላቅ ድርጅቶች በእርሻ ህብረት (ሲልስኮሳይዝ)

ውስጥ መታየታቸው የታወቀ ነው ። ከእነዚህም ውስጥ
ለምሳሌ የቃጫው ዋና ጣቢያ ጠቅላላውን የቃጫ አም
ራች ገበሬዎች ማህበሮችን ባንድ ላይ ይይዛል ። የቃ
ጫው ዋና ጣቢያ ለገበሬዎች ዘርና የእርሻ መሳሪያዎች
ይሰጣል ። ከዚያ በእነዚህ ገበሬዎች የተመረተውን
ቃጫ በሙሉ ይገዛል ። በብዛት ወደገበያ ይወስዳል ።
ለገበሬዎቹ ከትርፉ ውስጥ ድርሻቸውን እንደሚያገኙ
ዋስትና ይሰጣል ። በዚህም መንገድ በእርሻ አማካይነት
የገበሬ ኢኮኖሚንና የመንግስት ኢንዱስትሪን ያያይ
ዛል ። እንዲህ አይነቱን የምርት ድርጅት ምን ብለን
እንጥራው? በኔ ግምት በእርሻ መስክ በሀገር ውስጥ
የታላላቅ የመንግሥት ሶሻሊስት ምርት ስርአት ነው ።
ስለሀገር ውስጥ የመንግስት ሶሻሊስት ምርት ስርአት
ስናገር በካፒታሊዝም ስር ካለው የሀገር ውስጥ ስር
አት ሊመሳሰል ነው ። ለምሳሌ ያህል በጨርቃ ጨርቅ
ፋብሪካ እንደጠበብተኞቹ የጥሬ እቃዎቻቸውንና መሣ
ሪያዎቻቸውን ከካፒታሊስቱ በመውሰድ በመለስተኛ
ደመወዝተኛነት በራሳቸው ቤት ውስጥ በመስራት
ጠቅላላውን የስራቸውን ፍሬ ለእሱ የሚያስረክቡትን
ነው ። የእኛ እርሻ መዳበር የሚገነባበትን መንገድ ከሚ
ያሳዩ ብዙ መለኪያዎች አንዱ ይህ ነው ። በሌሎቹም
የእርሻ ክፍሎች ውስጥ ያሉ ተመሳሳይ መለኪያዎችን
እዚህ ላይ መጥቀሱ አስፈላጊ አይደለም ።

እጅግ ብዙ የሆኑ ገበሬዎች የግላዊ ካፒታሊስት
ላቲፋንዲያንና የደመወዝ ባርነትን ጎዳና ፣ የመራቆት
ንና የውድቀትን ጎዳና በመተው ይህንን አዲሱን ጎዳና
በደስታ እንደሚቀበሉት እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈ
ልገውም ።

ስለእኛ የእርሻ እድገት ጎዳና ሌኒን የሚለው
ይኸውና ፡—



"በሁሉም ታላላቅ የምርት ማከናወኛዎች ላይ
የመንግስት የበላይነት ፣ የመንግስት ስልጣን
በወዝአደሩ እጅ መሆን ፣ ከብዙ ሚሊዮን
ትናንሽና ፣ በጣም ትናንሽ ገበሬዎች ጋር
የዚህ ወዝአደር አጋርነት ፣ የወዝአደሩ መሪ
ነት በገበሬው መረጋገጥ ወዘተ. ከህብረት
ስራ ድርጅቶች ፣ ከነዚህ ድርጅቶች ብቻ የተሟ
ላ ሶሻሊስት ህብረተሰብ ለመገንባት የሚያስፈ
ልገው በሙሉ ይኸው አይደለም? እነዚህም
የህብረት ስራ ድርጅቶች ቀደም ብለን
እንደመገበያያ ድርጅቶች ፤ አድርገን በንቀት
ያየናቸውን አሁን በአዲሱ የኢኮኖሚ መመሪያ
(ኤን.ኢ.ፒ) ስር ከአንዳንድ አንፃር በንቀት
ልናያቸው የምንችል ናቸው ። ይህ ገና ሶሻ
ሊስት ህብረተሰብን መገንባት ሳይሆን
ለዚህ ለመገንባቱ አስፈላጊውና በቂውም
የሚሆነው ሁሉ ነው ።" (ቅጽ ፳፯ ፡ ገጽ
፫፻፺፪ ይመልከቱ ።)

በተጨማሪ በወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ስር
"እንደ አዲስ ህዝቡን የማደራጀት መርህና" ለህብ
ረት ስራ ማህበሮች የገንዘብና ሌላም እርዳታ መስጠት
ስለማስፈለጉ ሌኒን ሲናገር ፡—

"ማንኛውም የህብረተሰብ ስርአት የሚነሳው
በአንድ በተወሰነ መደብ የገንዘብ ድጋፍ
ብቻ ነው ። 'የነፃ' ካፒታሊዝም መወለድ
የሚያወጣውን በብዙ መቶ ሚሊዮን ሩብ
ሎች የሚቆጠር ዋጋ መጥቀስ አስፈላጊ አይ
ደለም ። አሁን ከተለመደው በላይ እርዳታ
የምንሰጠው የህብረተሰብ ስርአት ፤ የህብ

ረት ስራ ማህበር ስርአት የመሆኑን ሀቅ
መገንዘብና በገቢርም ማዋል አለብን ። ነገር
ግን እርዳታው የሚደረግለትም በቃሉ ትክ
ክለኛ አባባል ረገድ ነው ። ማለትም እርዳታ
የሚለውን ለማንኛውም አይነት የህብረት
ስራ ማህበር ንግድ እርዳታ ማድረግ ብሎ
መተርጎም በቂ አይሆንም ። እርዳታ ስንል
ከጠቅላላው ህዝብ እጅግ ብዙው ክፍል በር
ግጥ ተካፋይ ለሚሆንበት የህብረት ስራ ማህ
በር ንግድ እርዳታ ማድረግ ማለታችን ነው ።''
(ቅጽ ፳፯ ፡ ገጽ ፫፻፺፫ ይመልከቱ ።)

እነዚህ ሁሉ ሀቆች ምንን ያረጋግጣሉ?

የሚያረጋግጡት ተጠራጣሪዎቹ ትክክል እንዳል
ሆኑ ነው ። ሰፊውን ለፍቶ አዳሪ ገበሬ እንደ ወዝአደሩ
ደጋፊ በመቁጠሩ ሌኒኒዝም ትክክለኛ እንደሆነ ነው ።

እንዱስትሪን ከእርሻ ለማገናኘት ፣ የሶሻሊስት ስር
አት መገንባትን ለማራመድና ያለእሱ ወደ ሶሻሊስት
ኢኮኖሚ ለመሸጋገር የማይቻለውን አስፈላጊውን
መሠረት ለወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ለማቅረብ ፣ በስል
ጣን ላይ ያለው ወዝአደር ይህንን አጋር መጠቀም
ይችላል ፣ መጠቀምም አለበት ።

## ፪. የብሔር ጥያቄ

ከዚህ ዋና ሃሳብ ሁለት ታላላቅ ርእሶች እወስዳ
ለሁ ።

ሀ. የጥያቄው አቀራረብ ፤
ለ. የተጨቆኑ ህዝቦች የነፃነት እንቅስቃሴና
የወዝአደሩ አብዮት ፤



፩. <u>የጥያቄው አቀራረብ</u> ፡— ባለፉት ሀያ አመ
ታት በብሔር ጥያቄ ላይ በዛ ያሉ ታላላቅ ለውጦች
ተደርገዋል ። የብሔር ጥያቄ በሁለተኛው ኢንተርናሽናል
ጊዜና የብሔር ጥያቄ በሌኒኒዝም ጊዜ በጣም የተለያዩ
ናቸው ። ጠለቅ ባለ ሁናቴ እርስ በርስ ይለያሉ ። በአጠ
ቃላይ አመለካከት ብቻ ሳይሆን ከተፈጥሮ ባህርያቸው
ነው ።

ድሮ የብሔር ጥያቄ በተለይ ብዙውን ጊዜ "የሰ
ለጡ" ብሔረሰቦችን በሚመለከት ጠባብ አካባቢ ብቻ
የተወሰነ ነበር ። አይርሾች ፣ ሁንጌርያኖች ፣ ፓሊሾች ፣
ፊኒሾች ፣ ሰርቢያኖችና ሌሎችም በዛ ያሉ የአውሮፓ
ብሔረሰቦች እነዚህ ነበሩ እኩል ያልሆኑ ህዝቦች አካባ
ቢና የሁለተኛው ኢንተርናሽናል መሪዎችም ስለወደ
ፊት እድላቸው የተጨነቁላቸው ህዝቦች ። በመቶ ሚሊ
ዮን የሚቆጠሩና እጅግ አረመኔአዊና ጭካኔ በበዛበት
አይነት የብሔር ጭቆና የሚሰቃዩት የኢስያና የአፍሪካ
ህዝቦች ግን ብዙውን ጊዜ እነሱ ከሚመለከቱት አካባቢ
ውጪ ነበሩ ። ጥቁርና ነጭ የሆኑ "የሰለጠኑትንና"
"ያልሰለጠኑትን" በአንድ መስመር ላይ ማስቀመጡን
ያመኑቱበት ነበር ። ቅኝ ግዛቶችን ነፃ የማውጣትን ጥያቄ
ገሸሽ የሚያደርጉና ሁለት ወይንም ሶስት የሚሆኑ ትር
ጉም የሌላቸው ለዘብተኛ ውሳኔዎች ማሳለፍ-ይህ ብቻ
ነበር የሁለተኛው ኢንተርናሽናል መሪዎች የሚፎክሩ
በት ። አሁን በዚህ በብሔር ጥያቄ ላይ ማጭበርበርና
ልበሙሉ አለመሆን አክትሟል ልንል እንችላለን ።
ሌኒኒዝም ይህንን ግልጽ ከአካባቢው ውጪ የሆ
ነና ከጊዜው ጋር የማይስማማና የማይገጥም ነገር እር
ቃኑን አስቀረው ። በጥቁርና በነጭ ፤ በአውሮፓውያኖችና
በኢስያኖች "በሰለጠኑና" "ባልሰለጠኑ" የኢምፔሪያ

ሊዝም ባርያዎች መሀከል ያለውን ግንብ አፈረሰው
በዚህም ሁኔታ የብሔር ጥያቄን ከቅኝ ግዛት ጥያቄ ጋር
አያያዘው ። በዚሁ የብሔር ጥያቄን ከተወሰነና ውስጣዊ
ከሆነ የመንግስት ጥያቄ ወደ አጠቃላይና ኢንተርናሽ
ናል ጥያቄ ፣ በጥገኛና በቅኝ ግዛት ሀገሮች የሚገኙትን
የተጨቆኑ ህዝቦች ከኢምፔሪያሊዝም ቀንበር ነፃ ወደ
ማውጣቱ አለምአቀፍ ጥያቄ ተሸጋገረ ። የብሔሮች የራሳ
ቸውን እድል በራሳቸው የመወሰን መብት ድሮ ብዙውን
ጊዜ በተሳሳተ መንገድ ይተረጎም ነበር ። ብዙ ጊዜ
የብሔሮች የራሳቸው የውስጥ መብት (አቶኖሚ) ወደ
ሚለው ሃሳብ ጠበብ ይል ነበር ። አንዳንድ የሁለተኛው
ኢንተርናሽናል መሪዎች የብሔሮችን የራስን እድል በራስ
የመወሰን መብት ወደ የራስን ባህል ወደ መጠበቅ
መብት (ካልቸራል አቶኖሚ) እስከመለወጥ ድረስ እን
ኳን ሄደዋል ። ይህም ማለት የተጨቆኑት ብሔሮች የፖ
ለቲካ ስልጣኑን በሙሉ በገዢው መደብ እጅ በመተው
የራሳቸው የባህል ተቋሞች እንዲኖራቸው የመደረግ
መብት መሆኑ ነው ። ከዚህም የተነሳ የራስን እድል
በራስ የመወሰን መብት የመስፋፋት አላማን የመዋጊያ
መሳሪያ ከመሆን ይልቅ እንዲያውም ይህንኑ አላማ
ወደሚደግፍ መሳሪያነት የመለወጥ አደጋ ገጠመው ።
አሁን ይህ ውዥንብር ተጣርቷል ለማለት እንችላለን ።
ሌኒኒዝም የራስን እድል በራስ የመወሰን መብት ፅንሰ
ሃሳብ የተጨቆኑ የጥገኛና የቅኝ ሀገሮች ህዝቦች ፍጹም
የመገንጠል መብት ፤ የብሔሮች እንደ መንግስት በነፃ
የመኖር መብት ብሎ በመተርጎም አስፋፋው ። ይህ የራ
ስን እድል በራስ የመወሰን መብት የውስጥ አስተዳደር
መብት (አቶኖሚ) ብሎ በመተርጎም የመስፋፋት አላማ
መደገፍ የመቻሉን ሁኔታ ያስወግደዋል ። በዚህም ሁኔታ
የራስን እድል በራስ የመወሰን መርህ ራሱ በኢምፔሪ



ያሊስት ጦርነት ጊዜ ያለጥርጥር በሶሻል ሾቪኒስቶች
ሰፊውን ህዝብ ለማታለያ መሳሪያነት ይውል ከነበረ
በት አሁን ጠቅላላውን የኢምፔሪያሊስት ምኞትና የት
ምክህተኝነትን ሴራ ወደ ማጋለጫ መሳሪያነት ፤ ሰፊውን
ህዝብ በአለም አቀፋዊነት መንፈስ የፖለቲካ ትምህርት
ወደ መስጫ መሳሪያነት ተለወጠ ።

ድሮ የተጨቆኑ ብሔሮች ጥያቄ ብዙውን ጊዜ
ሙሉ በሙሉ የህግ (ጁሪዲካል) ጥያቄ እንደሆነ ይቆ
ጠር ነበር ። ስለ "ብሔራዊ የእኩልነት መብት" የሚደ
ረጉ ክቡር የሆኑ ውሳኔዎች ፣ ስለ "ብሔሮች እኩልነት"
የሚደረጉ ቁጥር ስፍር የሌላቸው ውሳኔዎች ፣ እነዚህ
የሁለተኛው ኢንተርናሽናል አይንን የሚስቡ የቃላቶች
ጋጋታ ናቸው ። ይህ የነሱ "የብሔሮች እኩልነት" አንዱ
የብሔሮች ቡድን (ንኡሳን) ሌላውን የብሔሮች ቡድን
በመበዝበዝ በሚኖረው በኢምፔሪያሊዝም ሥርዓት
ሥር በጭቁን ብሔሮች ላይ የሚደረግ ፌዝ የመሆኑን
ሀቅ ላይ ላዩን እየጋለቡ ማለፍ ነው ። አሁን ይህ በብ
ሔር ጥያቄ ላይ የቡርዧ ህጋዊ የሆነ የአመለካከት አቋም
ተጋልጦአል ለማለት እንችላለን ። ሌኒኒዝም የብሔርን
ጥያቄ እጅግ ከተመኛና ባለግርማ ከሆኑ ጉረኛ ውሳኔ
ዎች ጎትቶ ጠንካራ መሠረት ላይ አስቀመጠው ፤ የጭ
ቁን ብሔሮች የነፃነት ትግል በወዝአደሩ ፓርቲዎች
ቀጥታ እርዳታ ካልተደገፈ በስተቀር "ስለብሔሮች እኩ
ልነት" የሚደረግ ውሳኔ ትርጉም የሌለውና ሀሰት
እንደሚሆንም አስታወቀ ። በዚህም መንገድ የተጨቆኑ
ብሔሮች ጥያቄ የተጨቆኑ ብሔሮችን የመደገፍ ፣ ለብሔ
ሮች እርግጠኛ እኩልነት ፣ እንደ መንግስት በነፃ ለመ
ኖር ከኢምፔሪያሊዝም ጋር በሚያደርጉት ትግል እው
ነተኛና የማያቋርጥ ድጋፍ የመስጠት ጥያቄ ሆነ ።


7

ድሮ የብሔር ጥያቄ የሚታየው ከጥገና አንፃር
ነበር ። ይህም ማለት ከካፒታል ስልጣን አጠቃላይ
ጥያቄ ጋር ፤ ከኢምፔሪያሊዝም መወገድ ጋር ፤ ከወዝአደሩ
አብዮት ጋር ፤ ምንም ግንኙነት እንደሌለውና ብቻውን
እንደሚቆም ጥያቄ ተደርጎ ነበር ። በአውሮፓ ውስጥ
የወዝአደሩ አብዮት በቅኝ ግዛቶች ውስጥ ካለው
የነፃነት እንቅስቃሴ ጋር ቀጥተኛ የሆነ ትብብር ሳይ
ኖር ሊሳካ ይችላል ፤ የብሔር የቅኝ ግዛት ጥያቄ ከኢም
ፔሪያሊዝም ጋር አብዮታዊ ትግል ሳይደረግ ፤ ከወዝ
አደሩ አብዮት ጎዳና ሳይገጥም ፤ ያለግርግር "ከራሱ"
መፍትሄ ሊገኝለት ይችላል የሚል ስምምነት ውስጥ
ውስጡን ነበር ። አሁን ይህ ፀረ አብዮታዊ የሆነ አመለ
ካከት ተጋልጦአል ለማለት እንችላለን ። ሌኒኒዝም እን
ዳረጋገጠውና የኢምፔሪያሊስት ጦርነትና የሩሲያ አብ
ዮት እንዳጸደቁት የብሔር ጥያቄ መፍትሄ ሊያገኝ የሚ
ችለው ከወዝአደሩ አብዮት ጋር ሲያያዝና በእሱም ላይ
ሲመሰረት ብቻ ነው ። በምእራብ ውስጥ የሚካሄደው
አብዮት የድል ጎዳናም ያለው በኢምፔሪያሊዝም ላይ
የጥገኛና የቅኝ ግዛት ሀገሮች በሚያደርጉት ትግል በሚ
ኖረው አብዮታዊ ህብረት አማካይነት ነው ። የብሔር
ጥያቄ የወዝአደሩ አብዮት አጠቃላይ ጥያቄ ክፍል ፤
የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ጥያቄ ክፍል ነው ።

ጥያቄው እንደሚከተለው ነው ። በተጨቆኑ ሀገ
ሮች አብዮታዊ የነፃነት እንቅስቃሴ ውስጥ ሳይገለጡ
ያሉ አብዮታዊ ችሎታዎች ከአሁኑ ተሟጠው አልቀ
ዋል ወይስ አላለቁም? ካላለቁስ እነዚህን ችሎታዎች
ለወዝአደሩ አብዮት ፤ ጥገኛና ቅኝ የሆኑ ሀገሮችን ከኢ
ምፔሪያሊስት ቡርዧዎች ደጋፊነት ወደ አብዮታዊው



ወዝአደር ደጋፊነት ፤ ወደ ወዝአደሩ አጋርነት ለመለ
ወጥ አንዳች ተስፋ ፤ አንዳች መሠረት አለ?

ሌኒኒዝም በአወንታ ይመልሳል ። ይህም ማለት
በተጨቆኑ ሀገሮች የብሔራዊ ነፃነት እንቅስቃሴ ውስጥ
አብዮታዊ ችሎታዎች እንዳሉ ይቀበላል ። እነዚህንም
ችሎታዎች የጋራ ጠላት የሆነውን ኢምፔሪያሊዝምን
ለማስወገድ ለመጠቀም እንደሚቻልም ይገነዘባል ።
የኢምፔሪያሊዝም እድገት አካሄድ ፤ የኢምፔሪያሊስት
ጦርነትና የሩሲያ አብዮት በዚህ ነጥብ ላይ የሌኒኒዝ
ምን ማጠቃለያዎች ትክክለኛነት ሙሉ በሙሉ ያረጋግ
ጣሉ ።

ስለሆነም "የታላላቅ" ብሔሮች ወዝአደሮች የተ
ጨቆኑና ጥገኛ የሆኑ አገሮችን ብሔራዊ የነፃነት እንቅ
ስቃሴ መደገፍ ፤ በቁርጠኛነትና በንቁነት መደገፍ አለባ
ቸው ።

ይሁን እንጂ ይህ ማለት ወዝአደሩ ማንኛውንም
የብሔር እንቅስቃሴ ሁልጊዜና በሁሉም ቦታ ፤ በማንኛ
ውም በተናጠል ባለ ተጨባጭ ሁኔታ መደገፍ አለበት
ማለት አይደለም ። ሌኒኒዝም የሚለው ኢምፔሪያሊዝ
ምን ለመገልበጥ እንዲቻል እሱን ለሚያዳክሙ አይነት
ብሔራዊ እንቅስቃሴዎች ድጋፍ መስጠት ማለት እንጂ
ኢምፔሪያሊዝምን ለማጠንከር ወይንም ለማቆየት የሚ
ደረጉትን አይደለም ። አንዳንድ ጊዜ በአንዳንድ የተጨ
ቆኑ ሀገሮች ውስጥ ያሉ ብሔራዊ እንቅስቃሴዎች ከወዝ
አደራዊ እንቅስቃሴ እድገት ፍላጎቶች (ጥቅሞች) ጋር
የሚጋጩበት ጊዜ አለ ። እንዲህ ባለ ሁኔቴ ድጋፍ መስ
ጠት ፍጹም ከጥያቄ ውጪ ነው ። የብሔሮች መብት
ጥያቄ ብቸኛ የሆነ ፤ ራሱን የቻለ ጥያቄ አይደለም ።

የጠቅላላው የወዝአደሩ አብዮት ጥያቄ ክፍል ፣ ለጠቅ
ላላው ጥያቄ የበታች የሆነ ሲሆን መታየት ያለበትም
ከጠቅላላው የአመለካከት አንፃር ነው ። በ፲፰፻፵፰ ገደማ
ማርክስ የፖሊሾችንና የሁንጋርያኖችን የብሔር እንቅስ
ቃሴ ሲደግፍ የቼኮችንና የደቡብ ስላቮችን የብሔር እን
ቅስቃሴ ግን ይቃወም ነበር ። ለምን? ምክንያቱም በዚ
ያን ጊዜ ቼኮችና ደቡብ ስላቮች በአውሮፓ ውስጥ
"የሩሲያ የጥቃት ዘበኛ" ማለትም የፊላጭ ቆራጭ
ነት የጥቃት ጠባቂ ዘበኛ ስለነበሩ "አድሃሪ ህዝቦች"
ነበሩ ። ፖሎችና ሁንጋሪያኖች ግን ፈላጭ ቆራጭነትን
የሚዋጉ "አብዮታዊ ህዝቦች" ነበሩ ። ምክንያቱም
ያኔ የቼኮችንና የደቡብ ስላቮችን የብሔር እንቅስቃሴ
መደገፍ በተዘዋዋሪ መንገድ በአውሮፓ ውስጥ የአብዮ
ታዊ እንቅስቃሴዎች እጅግ አደገኛ ጠላት የሆነውን
ንጉሣዊ አገዛዝን ከመደገፍ እኩል ነበር ።

"የዲሞክራሲ የተለያዩ ጥያቄዎች (ዲማንድስ) ፣
የራስን እድል በራስ የመወሰን መብትም
ጭምር ፍጹም አይደሉም ፤ የጠቅላላው
የዓለም ዲሞክራሲያዊ (አሁን የጠቅላላው ሶሻ
ሊስት ) እንቅስቃሴ ትናንሽ ክፍሎች እንጂ ።
በአንዳንድ ተጨባጭ ሁኔታዎች የመላው
አካል ክፍልፋይ ከመላው አካል ሊቃረን ይች
ላል ። ይህ ከሆነ መቀበል አያስፈልግም ።"
(ሌኒን ፣ ቅጽ ፲፱ ፣ ገጽ ፪፻፵፯ ይመልከቱ ።)

የተወሰኑ ብሔራዊ እንቅስቃሴዎችንና የእነዚህን
እንቅስቃሴዎች ምንልባት የአድሀሪነትን ባህርይ በሚያ
ሳይ ወይንም በሚያመለክት ረገድ ባለው ጥያቄ ላይ የሚኖ
ረው አቋም ያህ ነው ። ይህም እንዲሁ ከታይታይ (ፎር



ማል) የአመለካከት አንፃር ፣ ተጨባጭ ካልሆነ ከረቂቅ
መብቶች አንፃር አመዛዝኖ በማየት ሳይሆን ከአብ
ዮታዊ እንቅስቃሴ ጥቅሞች አንፃር በመመልከት ነው ።

ስለጠቅላላው ብሔራዊ እንቅስቃሴዎች አብዮታዊ
ባህርይም እንዲሁ ማለት ያስፈልጋል ። ልክ በአንዳንድ
የተወሰኑ ብሔራዊ እንቅስቃሴዎች የአድሀሪነት ጠባይ
ሊኖር የመቻሉን ያህል የብዙሀኑ ብሔራዊ እንቅስቃሴ
ዎች የማያጠራጥር አብዮታዊ ባህርይም እንዲሁ ልዩ
ነው ። በኢምፔሪያሊስት የጭቆና ሁኔታ ስር የሚካሄ
ደው የብሔራዊ እንቅስቃሴ አብዮታዊ ባህርይው ፣ ወዝ
አደራዊ ክፍሎች በእንቅስቃሴው ውስጥ መኖራቸውን
ለእንቅስቃሴው አብዮታዊ ወይንም ሪፑብሊካዊ ፕሮግ
ራም መኖሩን ፣ ለእንቅስቃሴው ዲሞክራታዊ መሠረት
መኖሩን አስቀድሞውኑ የግዴታ አያስመለክትም ። ለአ
ፍጋኒስታን ነፃነት የአፍጋኒስታኑ ኤሚር የሚያደርገው
ትግል ፣ ኤሚሩና ተከታዮቹ ዘውደኛ (ሞናርኪስት)
አስተሳሰብ ቢኖራቸውም እንኳን ፣ በተጨባጭ ሁናቴ
ሲታይ አብዮታዊ ትግል ነው ። ምክንያቱም ኢምፔሪ
ያሊዝምን ያዳክመዋል ፣ ይበታትነዋል ፣ ያመነምነዋል ።
በሌላ በኩል ግን ለምሳሌ እንደ ክሬንስኪ ፣ ፀረቴሊ ፣
ሬናውደልና ሽይድማና ፣ ቼርኖብና ዳን ፣ ሄንደርሰንና
ክላይንስ ያሉ "ተስፋ የቆረጡ" ዲሞክራቶችና "ሶሻ
ሊስቶች" ፣ "አብዮተኞችና" ሪፑብሊካኖች በኢምፔሪ
ያሊስት ጦርነት ጊዜ ያደረጉት ትግል አድሀሪ ትግል
ነበር ። ምክንያቱም ውጤቱ የኢምፔሪያሊዝም መቆን
ጃጀት ፣ መጠናከርና ድል ማድረግ ነበርና ነው ። በተ
መሳሳይ ምክንያት የግብፃውያን ነጋዴዎችና ቡርዣ
ምሁራን ለግብፅ ነፃነት ሲሉ የሚያካሄዱት ትግል የግ
ብፅን ብሔራዊ እንቅስቃሴ መሪዎች ከቡርዧ የመነጩ ፣

የቡርዧ መጠሪያ ያላቸውና ሶሻሊዝምን ቢሆኑም እንኳን በተጨባጭ መልኩ ሲታይ የሚቃወሙ ትግል ነው ። ነገር ግን የእንግሊዝ "ሌበር" ፓርቲ <u>አብዮታዊ</u> የግብፅን የጥገኝነት አቋም እንዳለ አድርጎ ለማቆየት የሚያደርገው ትግል የዚህ መንግሥት አባሎች ከወዝ አደሩ የመነጩ ፣ ወዝአደራዊ መጠሪያ ቢኖራቸውም ፣ ለሶሻሊዝም "የቆሙ" ቢሆኑም <u>አድሀሪ</u> ትግል ነው ። በሌሎች ታላላቅ ቅኝና ጥገኛ ሀገሮች ለምሳሌ ህንድ ፣ ቻይና ውስጥ ያሉትን ብሔራዊ እንቅስቃሴዎች መጥቀሱ አያስፈልግም ። ማንኛውም በነፃነት ጎዳና የሚወሰድ እርምጃ ከአንዳንድ ለይስሙላ ከሚቀርቡ የዲሞክራሲ ጥያቄዎች ጋር የሚቃረን እንኳን ቢሆንም በኢምፔሪያሊዝም ላይ የሚደረግ ከፍተኛ ምት ነው ። ይህም ያለጥርጥር <u>አብዮታዊ</u> እርምጃ ነው ።

ሌኒን "የተጨቆኑ ሀገሮች ብሔራዊ እንቅስቃሴ መታየት ያለበት ከታይታይ ዲሞክራሲ አንፃር ሳይሆን ከኢምፔሪያሊዝም ጋር በሚደረገው ትግል ጠቅላላ የሰንጠረዥ ሚዛን (ባላን ስሽት) ላይ በሚታዩት የተጨበጡ ውጤቶች አንፃር ነው ሲል ትክክል ነበር ። ይህም ማለት "በተናጠል በብቸኝነት ሳይሆን በዓለም አቀፍ ደረጃ" ማየት ማለት ነው ። (ቅጽ ፲፱ ፣ ገጽ ፭፻፶፯ ይመልከቱ ።)

፪. <u>የተጨቆኑ ህዝቦች የነፃነት እንቅስቃሴና የወዝአደሩ አብዮት</u> ፦ የብሔር ጥያቄን ለመፍታት ሌኒኒዝም ከሚከተሉት ቲሰሶች ይነሳል ።

ሀ. ዓለም በሁለት ሠፈሮች (ካምፖች) ተከፍላለች ። ይህም የፈናንስ ካፒታል ያላቸውና



የዓለምን እጅግ ብዙሀን ህዝቦች የሚበዘብዙ እፍኝ የማይሞሉ የሠለጠኑ ብሔሮች ሠፈርና የብዙሀኑን ክፍል የሚይዝ በጥገኛና ቅኝ ሀገሮች የሚገኙ የተጨቆኑ የተበዘበዙ ህዝቦች ሠፈር ።

ለ. በፈናንስ ካፒታል የሚጨቆኑና የሚበዘበዙት ጥገኛና ቅኝ ሀገሮች ለኢምፔሪያሊዝም እጅግ ከፍተኛ ድጋፍና ፣ (ሪዘርቭ) እጅግ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው የጥንካሬው ምንጭ ናቸው ።

ሐ. በጥገኛና በቅኝ ሀገሮች ውስጥ የተጨቆኑ ህዝቦች በኢምፔሪያሊዝም ላይ የሚያካሄዱት አብዮታዊ ትግል ከጭቆናና ከብዝበዛ ወደ ነፃነታቸው የሚመራቸው ብቸኛው ጎዳና ነው ።

መ. እጅግ ከፍተኛ የሆኑ ቅኝና ጥገኛ ሀገሮች ከአሁኑ የብሔር ነፃነት እንቅስቃሴ ጎዳና ተከትለዋል ። ይህም የግዴታ ወደ ዓለም ካፒታሊዝም ቀውስ ማምራቱ አይቀርም ።

ሰ. በእድገት በደረጁ ሀገሮች ውስጥ ያለ የወዝአደሩ እንቅስቃሴ ጥቅምና በቅኝ ሀገሮች ውስጥ ያለ የነፃነት እንቅስቃሴ ፣ እነዚህ ሁለት አብዮታዊ እንቅስቃሴዎች በጋራ ጠላታቸው በኢምፔሪያሊዝም ላይ መተባበራቸውን ይጠይቃል ።

ረ. አብዮታዊ የጋራ ግንባር ካልተቋቋመና ካልተጠናከረ በስተቀር በእድገት በደረጁ ሀገሮች የሠራተኛው መደብ ማሸነፍና የተጨቆኑ ህዝቦች ከኢምፔሪያሊዝም ቀንበር ስር ነፃ መውጣት የማይቻል ነገር ነው ።

ሸ. የጨቋኝ ብሔሮች ወዝአደር የተጨቆኑ ህዝቦች "በእሱ ሀገር" ኢምፔሪያሊዝም ላይ በሚያደርጉት የነፃነት እንቅስቃሴ ቀጥተኛና ቁርጠኛ ድጋፍ ካልሰጠ በስተቀር አብዮታዊ የጋራ ግንባር ማቋቋም የማይቻል ነው ። ምክንያቱም ኤንግልስ እንደሚለው ፤ "ሌሎች ብሔሮችን ከጨቆነ ማንኛውም ብሔር ነፃ ሊሆን አይችልም ።"

ቀ. ይህም ድጋፍ የሚያመለክተው ብሔሮች የመገንጠላቸውን ፤ እንደ መንግስት በነፃ የመኖራቸውን መብት መፈክር ይዞ መነሣትን ፤ ለእሱ መሟገትን ፤ በሥራ መተርጎምን ነው ።

በ. ይህ መፈክር በተግባር ካልተተረጎመ በስተቀር ለሶሻሊዝም አለምአቀፍ ድል ቁስ አካላዊ መሠረት በሆነው በአለምአቀፍ የኢኮኖሚ ሥርዓት ውስጥ የብሔሮችን አንድነትና ትብብር ለማስገኘት አይቻልም ።

ተ. ይህም ህብረት ሊሆን የሚችለው በመፈቃቀድ ብቻ ሲሆን የሚመጣውም እርስ በርስ ከመተማመንና በህዝቦች መሀከል የወንድማማችነት ግንኙነት ከመኖሩ ነው ።

ከዚህም የተነሳ ሁለቱ ገጾች ፤ ሁለቱ የብሔር ጥያቄ አዝማሚያዎች እንዲህ ናቸው ፤ መጀመሪያ ከኢምፔሪያሊዝም ሰንሰለት ወደ ፖለቲካ ነፃነትና ነፃ የሆነ ብሔራዊ መንግሥት የመመሥረት አዝማሚያ ። ይህም ከኢምፔሪያሊስት ጭቆናና ከቅኝ ግዛታዊ ብዝበዛ ምክንያት የመጣ አዝማሚያ ነው ። ሌላው ከአለምአቀፍ ገበያና ከአለም የኢኮኖሚ ሥርዓት መመሥረት የተነሳ የመጣው በብሔሮች መሀከል የቀረበ የኢኮኖሚ ግንኙነት ነው ።



"በማደግ ላይ ያለ ካፒታሊዝም በብሔር ጥያቄ ላይ ሁለት ታሪካዊ አዝማሚያዎች ያውቃል ። መጀመሪያ ብሔራዊ ኑሮና ብሔራዊ እንቅስቃሴዎች በሁሉም ብሔራዊ መንግሥቶች ላይ ትግልን መቀስቀስ ፤ ሁለተኛ በብሔሮች መሀከል የእድገትና በየጊዜው የሚጨምር የሁሉም አይነት ግንኙነቶች መኖር ፤ የብሔራዊ ድንበሮች መፍረስ ፤ የካፒታል ፤ የጠቅላላ ኢኮኖሚ ኑሮ ፤ የፖለቲካ ፤ የሳይንስ . . .ወዘተ ኢንተርናሽናል የሆነ አንድነት መፈጠር ።

"ሁለቱም አዝማሚያዎች የካፒታሊዝም ሁለንታዊ ህጎች ናቸው ። የመጀመሪያው በእድገት መጀመሪያ ላይ የገነነ ይሆናል ። ሁለተኛው የበሰለንና ወደ ሶሻሊስት ህብረተሰብ ወደ መለወጡ በመገስገስ ላይ ያለን ካፒታሊዝም ያሳያል ይላል ሌኒን ። (ቅጽ ፳፪ ፤ ገጽ ፩፻፴፱—፩፻፵ ይመልከቱ ።)

ለኢምፔሪያሊዝም እነዚህ ሁለቱ አዝማሚያዎች ሁለት የማይታረቁ ቅራኔዎችን ያሳያሉ ። አንድም ኢምፔሪያሊዝም ቅኝ ግዛቶችን ሳይበዘብዝና "በአንድ የተሟላ" አጠቃላይ መዋቅር ውስጥ በሀይል ይዞ ሳያቆያቸው ሊኖር አይችልም ። ምክንያቱም ኢምፔሪያሊዝም ብሔሮችን አንድ ላይ ሊያመጣቸው የሚችለው ግዛቱን በማስፋፋትና በቅኝ ግዛት ወረራ ስለሆነ ነው ። በአጠቃላይ ስንናገር የእምፔሪያሊዝም ያለእዚህ መኖር የማይታሰብ ነው ።

በተቃራኒ ግን እነዚህ ሁለቱ አዝማሚያዎች ኮሚኒዝም ላለው አንድ አላማ የሚሆኑ ሁለት ገጾች ናቸው ። የተጨቆኑ ህዝቦችን ከኢምፔሪያሊዝም ቀንበር ሥር

ነፃ ለማውጣት አላማ ምክንያቱም በአንድ አለምአቀፍ የኢኮኖሚ ሥርዓት ውስጥ የህዝቦች አንድነት ሊኖር የሚችለው እርስ በእርስ በመተማመንና በመፈቃቀድ የስምምነት መሠረት ላይ ሲሆንና ፣ ህዝቦች በገዛ ፈቃዳቸው አንድነትን የሚፈጥሩበት ጎዳና ያለውም ቅኝ ግዛቶችን ከኢምፔሪያሊስት "የተሟላ" ሥርዓት በመነጠልና ቅኝ ግዛቶችን ወደ ነፃ መንግሥቶች በመለወጥ መሆኑን ኮሚኒዝም ያውቃል ።

ይህም በመሆኑ በገዥ ብሔሮች (ብሪታንያ ፣ ፈረንሳይ ፣ አሜሪካን ፣ ኢጣሊያን ፣ ጃፓን . .ወዘተ) ውስጥ ባሉ "ሶሻሊስቶች" የገናና ብሔር ትምክህተኝነት ላይ የማያቋርጥ ቁርጠኛ የሆን ትግል ማካሄድ ያስፈልጋል ። እነዚህ የራሳቸውን ኢምፔሪያሊስት አገዛዞች ለመዋጋት የማይፈልጉ ፣ "በራሳቸው" ቅኝ ግዛቶች ውስጥ የተጨቆኑ ህዝቦች ከጭቆና ነፃ ለመውጣትና ለመገንጠል በሚያደርጉት ትግል ሊረዱአቸው የማይፈልጉ ናቸው ።

ያለ እንደዚህ ያለ ትግል የገዥ ብሔሮችን የሠራተኛ መደብ በእውነተኛ ኢንተርናሽናሊዝም መንፈስ ፣ በቅኝና በጥገኛ ሀገሮች ካሉት ከሰፊው ሠርቶ አደር ህዝቦች ጋር በተቀራረበ ግንኙነት መንፈስ ፣ ለወዝአደሩ አብዮት በእርግጥ የመዘጋጀት መንፈስ ለማስተማር በፍጹም አይቻልም ። የሩሲያ ወዝአደር ከድሮው የሩሲያ ግዛት (ኤምፓየር) ጭቁን ህዝቦች መተሳሰብንና መስማማትን ባያገኝ ኖሮ በሩሲያ ውስጥ አብዮቱ አሸናፊ ሊሆን አይችልም ነበር ። ኮልቻክና ዴንኪንም አይደመሰሱም ነበር ። ነገር ግን የእነዚህን ህዝቦች የመተሳሰብንና የመደጋገፍን በጎ ፈቃድ ለማግኘት የሩሲያ ወዝአደር አስቀድሞ የሩሲያ ኢምፔሪያሊዝምን ሰንሰለት መበጠስና እነዚህን ሰዎች ከብሔር ጭቆና ቀንበር ማላቀቅ ነበረበት ።



ያለዚህ የሶቭየት ሥልጣንን ለማጠናከር ፤ እውነተኛ ኢንተርናሽናሊዝምን ለመመሥረትና ለወደፊቱ የሰዎች በአንድ አለምአቀፍ የኤኮኖሚ ሥርዓት ሥር መዋሀድ ቋሚ ምሳሌ የሚሆነውን የሶቭየት ህብረት ሶሻሊስት ሪፑብሊክ ተብሎ የሚጠራውን ተደናቂ ድርጅትን ለሰዎች ትብብር ብሎ መፍጠር አይቻልም ነበር ።

ከዚህም የተነሣ በተጨቆኑ ሀገሮች ውስጥ ያሉ ሶሻሊስቶች የብሔር ብቸኝነትን ፤ (አይሶሌሺኒዝም) ጠባብነትንና ከሌላ መራቅን የግዴታ መታገል ያስፈልጋል ። እነዚህም ከራሳቸው ጠባብ ብሔረተኝነት በላይ ከፍ ለማለት የማይፈልጉና በራሳቸው ሀገሮች ውስጥ ባለው የነፃነት እንቅስቃሴና በገዥ ሀገሮች ውስጥ ባለው ወዝአደራዊ እንቅስቃሴ መሀከል ያለውን ግንኙነት ያልተረዱ ናቸው ።

ያለእንደዚህ ያለ ትግል የጭቁን ብሔር ወዝአደሮች የጋራ ጠላትን ለመገልበጥ በሚደረገው ትግል ፣ ኢምፔሪያሊዝምን ለመገልበጥ በሚደረገው ትግል ከገዥ ሀገሮች ወዝአደሮች ጋር ነፃ የሆን መመሪያና የመደብ አንድነትን ለመጠበቅ ይችላሉ ብሎ ለመገመት አይቻልም ።

ያለእንደዚህ አይነት ትግል ኢንተርናሽናሊዝም የማይቻል ይሆናል ። የጨቋኝና የተጨቋኝ ብሔሮችን ሰፊ ለፍቶ አደር ህዝብ በአብዮታዊ ኢንተርናሽናሊዝም መንፈስ የማስተማሪያ መንገዱ ይህ ነው ።

ሠራተኞችን በኢንተርናሽናሊዝም መንፈስ በማስተማር በኩል ስላለው የኮሚኒዝም እጥፍ ተግባር ሌኒን የሚከተለውን ይላል ።

“. . . በታላላቅ ጨቋኝ ብሔሮችና
የተጨቆኑ ብሔሮች ፡ ግዛታቸውን በትናንሽ
ተው የሌላውን በሚይዙና ግዛታቸው አስፋፍ
በተያዘው ብሔሮች . . .እንዲህ ያለው በሌላ
ርት ሙሉ በሙሉ አንድ አይነት ትምህ
ይችላል? በፍጹም አይሆንም ። እዚህ ላይ ሊሆን
ዋነኛው ግብ የሚወስደው መንገድ ወደ ፍጹም ወደ
እኩልነት ፡ በጣም ወደተቀራረበ ግንኙነት
ብሎም የሁሉም ብሔሮች መቀላቀል የሚያ
መራው በእያንዳንድ ተጨባጭ ሁናቴ በተለያየ
መስመር መሆኑ ግልጽ ነው ። በምሳሌ
ለመግለጽ ያህል በአንድ ገጽ መሀል ላይ
ወደአለች ነጥብ የሚወስደው መስመር ከአንዱ
ጠርዝ ወደ ግራ ሲሆን ከሌላው ተቃራኒ ጠርዝ
ደግሞ ወደ ቀኝ እንደሚሆን አይነት ነው ።
የአንድ ታላቅ ፡ ጨቋኝና የሌላ ግዛት
በሀይል የሚይዝ ብሔር አባል የሆነ ሶሻል
ዲሞክራት በአጠቃላይ ስለብሔሮች መቀላቀል
እየሰበከ ፡ “የሱ” ዳግማዊ ኒኮላስ ፡ “የሱ” ዊል
ሄልም ፡ ጆርጅ ፓይንኬር. . .ወዘተ. ጭምር
ከታናናሽ ብሔሮች ጋር መቀላቀልን እንደሚ
ደግፉ (ወረው በመያዝ) ዳግማዊ ኒኮላ ከጋሊ
ሺያ ጋር “መቀላቀልን” እንደሚደግፍ ፡
ዳግማዊ ዊልሄልም ከቤልጂግ ጋር “መቀላ
ቀልን” እንደሚደግፍ. . .ወዘተ. ለአንዲት
ደቂቃ እንኳን ከረሳ እንዲህ አይነቱ ሶሻል
ዲሞክራት በቲዎሪ ፍሬቢስና አስቂኝ ዶክት
ሪኔር ሲሆን በተግባር የኢምፔሪያሊዝም
ተባባሪ ይሆናል ።



“በጨቋኝ ሀገሮች ውስጥ ላሉ ሠራተኞች
የሚቀርበው ኢንተርናሽናሊስት ትምህርት
ማተኮር ያለበት የተጨቆኑ ሀገሮችን የመገን
ጠል መብት እንዲደግፉና እንዲሰብኩ
በሚያበቃቸው ላይ ነው ። ያለ እዚህ ኢንተር
ናሽናሊዝም ሊኖር አይችልም ። እንዲህ
አይነቱን ፕሮፓጋንዳ ከማካሄድ የሚቆጠበ
ውን የማንኛውንም የጨቋኝ ብሔር ሶሻል
ዲሞክራት እንደ ኢምፔሪያሊስትና አጭበር
ባሪ አድርገን መቁጠር መብታችንም ተግባራ
ችንም ነው ። ምንም እንኳን ሶሻሊዝም ከመ
መሥረቱ በፊት የመገንጠል እድል ከሺህ
አንድ ብቻ “ሊሆን የሚችል ቢመስልም”. . .
ይህ ፍጹም የሆነ ግዴታ ነው ።

“በሌላ በኩል በትንሽ ተጨቋኝ ፡ ብሔር ውስጥ
የሚገኝ ሶሻል ዲሞክራት በቅስቀሳው ላይ
የአጠቃላይ ፎርሙላዎችን ሁለተኛው ቃል የሆ
ነውን የብሔሮች “ፈቅዶ መቀላቀል” የሚለ
ውን ማጥበቅ አለበት ። የኢንተርናሽናሊስት
ተግባሮችን ሳይጥስ ወይ ለራሱ ብሔር ለፖ
ለቲካ ነፃነት ድጋፉን ሊሰጥ አለዚያም
የጎረቤት ሀገር ከሆነው ከሀ. ለ. ሐ. . . ወዘተ.
ጋር መቀላቀልን ሊደግፍ ይችላል ። ነገር ግን
በሁሉም አኳኋን የትንሽ ብሔርን ጠባብ አስ
ተሳሰብ ፡ ብቸኝነትንና ከሌላው መራቅን መዋ
ጋት አለበት ። ለመላውና ለአጠቃላይ አንድነት
መታወቅ መታገል አለበት ። የተወሰነው
ክፍል ጥቅሞች ለአጠቃላይ ጥቅሞች የበታች
እንዲሆኑ መታገል አለበት ።

"ጥያቄውን ሙሉ በሙሉ ያልተመለከቱ ሰዎ
ች በጨቋኝ ብሔሮች ውስጥ ያሉ ሶሻል
ዲሞክራቶች "ለመገንጠል ነፃነት" አጥብ
ቀው ሲቆሙ ፣ በተጨቆኑ ብሔሮች ውስጥ
ያሉ ሶሻል ዲሞክራቶች ደግሞ "ለመቀላ
ቀል ነፃነት" አጥብቀው ሲቆሙ በመሀከላ
ቸው "ቅራኔ" አለ ብለው ያስባሉ ። ይሁን
እንጂ ነገሩን ጥቂት አዞሮ ማየት ወደ ብሔ
ሮች ጥያቄ ግብ ለመድረስ ምንም ሌላ
አማራጭ መንገድ እንደሌለ ፣ ካለው ተጨ
ባጭ ሁኔታ ተነስቶ ወደ ኢንተርናሽናሊዝ
ምና ወደ ብሔሮች መቀላቀል የሚያመራ
ከዚህ የተለየ ምንም ሌላ መንገድ እንደሌ
ለና ሊኖርም እንደማይችል ያሳያል ።"
(ቅጽ ፲፬ ፣ ገጽ ፱፻፳፩—፱፻፳፪ ይመልከቱ ።)

## ፯. ስትራቴጂና ታክቲክ

ከዚህ ዋና ሃሳብ ስድስት አርእስቶች እወስዳለሁ ።

ሀ. ስትራቴጂና ታክቲክ የወዝአደሩን የመደብ ትግል እንደሚመራ ሳይንስ ፤

ለ. ስትራቴጂና የአብዮቱ ደረጃዎች ፤

ሐ. ታክቲክና የእንቅስቃሴው ውጣ ውረድ ፤

መ. ስትራቴጂካዊ መሪነት ፤

ሠ. ታክቲካዊ መሪነት ፤

ረ. ጥገናዊነትና አብዮታዊነት ።



፩. ስትራቴጂና ታክቲክ የወዝአደሩን የመደብ
ትግል እንደሚመራ ሳይንስ ፤ በሁለተኛው ኢንተርና
ሽናል የበላይነት በነበረው ጊዜ ይብዛም ይነስ
ሰላማዊ የእድገት ሁኔታዎች ባሉበት ሁኔታ ስር የወዝ
አደሩን የፖለቲካ ሠራዊቶች የማቋቋምና የማሠልጠን
ጊዜ ነበር ። ጊዜው ፓርላማዊነት እንደ ከፍተኛው አይ
ነት የመደብ ትግል የነበረበት ጊዜ ነበር ። ስለትላልቅ
የመደብ ግጭቶች ፣ ወዝአደሩን ለአብዮታዊ ግጭቶች
ስለማዘጋጀትና የወዝአደሩን የበላይ ገዥነት ስለማስገ
ኘት የሚቀርቡ ጥያቄዎች ያኔ የጊዜው ተግባር መስ
ለው አልታዩም ነበር ። የጊዜው ተግባር የወዝአደሩን
ሠራዊት ለማቋቋምና ለማሠልጠን ሲባል ማንኛውንም
አይነት ህጋዊ እድገት መጠቀም ፣ የወዝአደሩ አቋም
በነበረበት ደረጃ እንዲሁ ተቃዋሚ ሆኖ መቅረብ በሚ
ኖርበት ሁኔታ ፓርላማዊነትን መጠቀም ነበር ። በእን
ዲህ አይነት ጊዜና ስለወዝአደሩ ተግባሮች ካለው ከእ
ንዲህ አይነት ዕንሰ ሃሳብ ጋር የተሟላ ስትራቴጂም
ይሁን በሰፊው የተብራራ ታክቲክ ሊኖር እንደማይችል
እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ። ስለ ታክቲክና
ስትራቴጂ የተበጣጠሱና የተራራቁ ሃሳቦች ነበሩ ።
ይሁን እንጂ ታክቲክና ስትራቴጂ የሚባሉ አልነበሩም ።

የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ዋና ሀጢአቱ በዚያን
ጊዜ ፓርላማዊ የትግል አይነቶች የመጠቀም ታክቲክ
መከተሉ አልነበረም ። ሀጢአቱ የእነዚህን ዘዴዎች
ጠቃሚነት ከመጠን በላይ ማጋነኑ ፣ ሌላ አይነቶች እንደ
ሌሉና እነሱ ብቻ እንደሆኑ አድርጎ እስከመቁጠር መድ
ረሱ ፣ የግልጽ አብዮታዊ ጦርነቶች ጊዜ ሲመጣና ከፓ
ርላማ ውጪ የሚደረጉ የትግል አይነቶች ጥያቄ ግንባር
ቀደም ሆኖ ሲቀርብ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል

ፓርቲዎች በእነዚህ አዲስ ተግባሮች ላይ ፊታቸውን ማዞራቸውና መቀበልም እንቢ ማለታቸው ነበር ።

ከዚያ ቀጥለው በነበሩት ጊዜያት ማለትም በወዝ አደሩ የቀጥታ ድርጊት ተሳትፎ ጊዜ ፣ በወዝ የት ጊዜ ፣ ቡርዧውን የመገልበጥ ጥያቄ በወዝአደሩ አብ ተግባራዊ ድርጊት ጥያቄ በሆነበት ጊዜ ፣ የአስቸኳይ አብዮት ደጀን ጥያቄ (ስትራቴጂ) ከታላላቅ ጥያቄዎች አንዱ በሆነበት ጊዜ ፣ ሁሉም የትግል አይነቶች ፓርላ ማዊም ይሁን ከፓርላማ ውጪ (ታክቲክ) በግልጽ ራሳ ቸውን በገለጹበት ወይንም በተከሰቱበት ጊዜ ፤ በዚህን ጊዜ ብቻ ነበር ለወዝአደሩ ትግል የተሟላ ስትራቴጂና በሰፊው የተብራራ ታክቲክ ሊሠራ የተቻለው ። ሌኒን በሁ ለተኛው ኢንተርናሽናል አድርባዮች ታፍኖ የነበረውን የማርክስና የኤንግልስን ድንቅ የሆኑ ስትራቴጂና የታክ ቲክ ሃሳቦች በግልጽ ያወጣቸው በዚህን ጊዜ ነበር ። ይሁን እንጂ ሌኒን የማርክስና የኤንግልስን የተወሰኑ ታክ ቲካዊ ሃሳቦች (ፕሮፖዝሽንስ) እቦታቸው በመመለስ ብቻ አልተወሰነም ። ለወዝአደሩ የመደብ ትግል መሪነት ወደ አንድ የህግጋትና የመሪነት መርሆች ሥርዓት ውስጥ በማጠቃለል ፣ አዳዲስ ሃሳቦችንና አስተያየቶችን (ፕሮፖዚሽንስ) በማከል በይበልጥ አዳብሯል ። የሌኒን መጽሐፎች ለምሳሌ እንደ ምን መደረግ አለበት? ሁለት ታክቲኮች ፣ ኢምፔሪያሊዝም ፣ መንግሥትና አብዮት ፣ የወዝአደሩ አብዮትና ከሀዲው ካዎትስኪይ ፣ “ግራ ክንፍ” ኮሚኒዝም ፣ ያሉት ያለጥርጥር ለጠቅላላው የማርክሲ ዝም ሀብት ፣ ለአብዮታዊ መጋዘኑ ፣ (አርሴናል) እጅግ ከፍተኛ መዋጮ ናቸው ። የሌኒኒዝም ስትራቴጂና ታክቲክ የወዝአደሩን አብዮታዊ ትግል የሚመራውን ሳይንስ ይይዛል ።



፱. ስትራቴጂና የአብዮቱ ደረጃዎች ። ስትራቴጂ በአንድ በተሰጠ የአብዮቱ ደረጃ የወዝአደሩ ዋና ሀይል የሚከተለው ቁርጠኛ አቅጣጫ (መስመር ፣) ከዚሁ ጋር የሚገናዘብ የአብዮታዊ ሀይሎችን (ዋናና ተከታይ ሀይሎችን) አሰላለፍ (አቀማመጥ) የሚያዘጋጅ እቅድ በሰፊው ማብራራት ፣ በተሰጠው የአብዮቱ ደረጃ ይህን እቅድ ለመፈጸም መዋጋት ነው ።

የኛ አብዮት ከአሁኑ በሁለት ደረጃዎች ውስጥ አልፎአል ። ከጥቅምቱ አብዮት በኋላ ደግሞ ሶስተኛው ውስጥ ገብቷል ። የኛም ስትራቴጂ በዚሁ አኳኋን ተለ ዋውጦአል ።

የመጀመሪያው ደረጃ ፣ ከ፲፱፻፫ እስከ የካቲት ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ድረስ ያለው ሲሆን ዓላማው ፣ ንጉሳዊ አገዛዝን መገልበጥና የመካከለኛ ዘመን (ሚዲቫሊዝም) ርዝራዦችን ሙሉ በሙሉ ጠራርጎ መጣል ። የአብዮቱ ዋና ሀይል ፣ ወዝአደሩ ፣ ቅርብ ደጋፊው(ደጀን) ፣ ገበሬው ። የዋናው ሀይል ምት አቅጣጫ ፣ ገበሬውን ወደ ራሱ ስቦ ከንጉሳዊ አገዛዝ ጋር የመቻቻል ድርድር በማድረግ አብዮቱን ለመደምሰስ ይጥር የነበረውን ሊበራል (ለዘብተኛ) ዘው ደኛ ቡርዧውን ነጥሎ ብቸኛ ማድረግ ። የሀይ ሎች አቀማመጥ (አሰላለፍ) እቅድ ፣ የሠራ ተኛው መደብ ከገበሬው ጋር መተባበር ። የአንድን ሰው ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ቅዋሜ በሀይል ለማንኮታኮትና የቡርዧውን ወላዋ ይነት ለማሽመድመድ ወዝአደሩ ራሱን ከሰፊው ገበሬ ጋር በማስተባበር ዲሞክራ

ቲክ አብዮቱን ወደ ፍጻሜ ማድረስ አለ
በት።) (ሌኒን ቅጽ ፰ ፡ ገጽ ፶፯ ይመልከቱ።)

ሁለተኛው ደረጃ ፡ ከመጋቢት ፲፱፻፲፯
ምት ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ድረስ። አላማው ፡ ኢምፔሪያሊዝ
ምን ከሩሲያ ማስወገድና ከኢምፔሪያሊስት ጦርነት
ውስጥ መውጣት። የአብዮቱ ዋና ሀይል ፡ ወዝአደሩ።
የቅርብ ደጋፊው ፡ ደሀው ገበሬ። የጎረቤት ሀገሮች ወዝ
አደር እንደ የምናልባት (ፕሮባብል) ደጋፊ። የተራዘ
መው ጦርነትና የኢምፔሪያሊዝም ቀውስ እንደ አመቺ
ነጥብ። የዋናው ምት አቅጣጫ ለፍቶ አዳሪውን ሰፊ
ገበሬ ወደራሳቸው ለመውሰድና ከኢምፔሪያሊዝም ጋር
የመቻቻል ድርድር አድርገው አብዮቱን ለማብቃት
ይጥሩ የነበሩትን የንኡስ ከበርቴ ዲሞክራቶችን (ሜንሼ
ቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞችን) ነጥሎ ብቸኛ ማድረግ።
የሀይሎች አቀማመጥ (አሰላለፍ) እቅድ ፡ የወዝአደሩ
ከደሀው ገበሬ ጋር መተባበር።

"የቡርዧውን ቅዋሜ በሀይል ለማንኮታኮትና
የገበሬውን ፤ የንኡስ ከበርቴውን ወላዋይነት
ለማሽመድመድ ወዝአደሩ የህዝቡ ክፍል
ከሆኑት ከሰፊው መለስተኛ ወዝአደሮች
ጋር ራሱን በማስተባበር ሶሻሊስት አብዮትን
ማካሄድ አለበት።" (ቅጽ ፰ ፡ ገጽ ፶፮ ይመ
ልከቱ።)

ሶስተኛው ደረጃ ፡ ይህ የጀመረው ከጥቅምት አብ
ዮት በኋላ ነው። ዓላማው ፤ በሁሉም አገሮች ውስጥ
ኢምፔሪያሊዝምን ለማሸነፍ ሲባል እንደ መሠረት አድ
ርጎ በመጠቀም ይህን ዓላማ ለመምታት በአንድ ሀገር
ውስጥ የወዝአደሩን የበላይ ገዥነት ማጠናከር። አብዮቱ



ከመወሰን አልፎ ይስፋፋል። የአለም አብ
በአንድ ሀገር ከመወሰን አልፎ ይስፋፋል። የአለም አብ
ዮት ዘመን ይጀምራል። የአብዮቱ ዋና ሀይሎች ፡ በአ
ንድ ሀገር የወዝአደር የበላይ ገዥነት ፡ በሁሉም ሀገሮች
ውስጥ ያለ የወዝአደሩ አብዮታዊ እንቅስቃሴ። ዋና
ደጋፊ (ሪዘርቭ) ፡ በኢንዱስትሪ በዳበሩ ሀገሮች ያሉ
መለስተኛ ወዝአደሮችና ሰፊ ትናንሽ ገበሬዎች ፡
በቅኝና በጥገኛ ሀገሮች ያሉ የነፃነት እንቅስቃሴዎች።
የዋናው ምት አቅጣጫ ፡ ከኢምፔሪያሊዝም ጋር የመቻ
ቻል ድርድር መመሪያ ዋና ደጋፊዎች የሆኑትን የን
ኡስ ከበርቴ ዲሞክራቶች ነጥሎ ብቸኛ ማድረግ ፡ የሁ
ለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎችን ነጥሎ ብቸኛ
ማድረግ። የሀይሎች አቀማመጥ እቅድ ፡ የወዝአደሩ
አብዮት በጥገኛና ቅኝ ሀገሮች ውስጥ ካሉት የነፃነት
እንቅስቃሴዎች ጋር መተባበር።

ስትራቴጂ የሚጨነቀው በአብዮቱ ዋና ዋና ሀይ
ሎችና ደጋፊዎቻቸው (ሪዘርቭስ) ነው። አብዮቱ ከአ
ንዱ ደረጃ ወደሌላው ሲተላለፍ የሚለወጥ ሲሆን
በአንድ በተሰጠ ደረጃ ውስጥ ግን በመሠረቱ ሳይለ
ወጥ ይቆያል።

፫. ታክቲክና የእንቅስቃሴው ውጣ ውረድ።
ታክቲክ ከሌላው ሲወዳደር አጭር ጊዜ በሆነው በእን
ቅስቃሴው ውጣ ውረድ ፡ አብዮቱ ከፍ ወይንም ዝቅ
በሚልበት ጊዜ የወዝአደሩ አመራር መስመር ቁርጠኛ
ነት ፡ ይህንንም መስመር ለማካሄድ አሮጌ የድርጅትና
የትግል ዘዴዎችን በአዳዲስ ፡ አሮጌ መፈክሮችን በአዳ
ዲስ በመተካትና እነዚህን በማዋሀድ . . . ወዘተ. የሚደ
ረገው ትግል ነው። የስትራቴጂ ዓላማ በንጉሳዊ አገ
ዛዝ ላይ ወይንም እንበል በቡርዧው ላይ የሚደረገ
ውን ጦርነት ማሸነፍ ፡ በንጉሳዊ አገዛዝ ላይ ወይንም

በቡርዧው ላይ የሚደረገውን ትግል እስከ ፍፃሜ ማድ ረስ ሲሆን ታክቲኮች ግን ከዚህ አነስ ያለ ዓላማን ይከተ ላሉ ። ምክንያቱም ዓላማቸው ጠቅላላውን ጦርነት ማሸ ነፍ ሳይሆን አንዳንድ የተወሰኑ ግጥሚያዎችን ፣ የተወሰኑ ውጊያዎችን ማሸነፍ ፣ በአንድ በተሰጠ አብዮቱ ከፍ ወይንም ዝቅ በሚልበት ጊዜ ከተጨባጭ ሁናቴዎች ጋር የሚገናዘቡ አንዳንድ የተወሰኑ ዘመቻዎችን ወይ ንም ድርጊቶችን በተሳካ ሁኔታ ማካሄድ ነው ። ታክቲ ኮች የስትራቴጂ ክፍል ፣ የእሱ ተከታይና እሱንም የሚ ያገለግሉ ናቸው ።

ታክቲኮች እንደ ውጣ ውረድ ይለወጣሉ ። በመጀ መሪያው የአብዮቱ ደረጃ ጊዜ (፲፱፻፷ እስከ የካቲት ፲፱፻፷፯) የስትራቴጂ እቅድ ሳይለወጥ ሲቆይ ታክቲኮች በዚህን ጊዜ ውስጥ ብዙ ጊዜ ተለዋውጠዋል ። ከ፲፱፻፷ እስከ ፲፱፻፷፰ ዓ. ም. ድረስ በነበረው ጊዜ ፓርቲው የማጥቃት ታክቲኮች ይከተል ነበር ። ምክንያቱም የአብ ዮቱ ማእበል እያደገ ነበር ። እንቅስቃሴው እያሻቀበ ይሄድ ነበር ። ታክቲኮችም ከዚህ ሀቅ መነሳት ነበረባቸው ። ከዚህም የተነሳ ከፍ እያለ የሚሄደው የአብዮቱ ማእበል ከሚጠይቀው ሁናቴ ጋር በመገናዘብ የትግል ዘዴዎ ችም አብዮታዊ ነበሩ ። የቀበሌ የፖለቲካ የስራ ማቆም አድማዎች ፣ የፖለቲካ ሰላማዊ ሰልፎች ፣ አጠቃላይ የፖለቲካ የስራ ማቆም አድማ ፣ ዱማ ውስጥ አለመሳ ተፍ ፣ አመፅ ፣ አብዮታዊ የሆኑ መፈክሮች ፣— በዚያን ጊዜ ተከታታይ የነበሩ የትግል አይነቶች እንዲህ ነበሩ ። በትግል አይነቶች ውስጥ ያሉ እነዚህ ለውጦች በአንፃ ራቸው ከሚደረጉት የድርጅት ለውጦች ጋር አብረው ይሄዱ ነበር ። የፋብሪካ ኮሚቴዎች ፣ አብዮታዊ የገበሬ ኮሚቴዎች ፣ የስራ ማቆም አድማ ኮሚቴዎች ፣ የሶቭየት የሰራተኞች ተወካዮች ፣ ከሞላ ጎደል በግልጽ የሚሰራ



የሰራተኞች ፓርቲ ። በዚያን ጊዜ የነበሩ የድርጅት አይ ነቶች እንዲህ ነበሩ ።

ከ፲፱፻፷፰ እስከ ፲፱፻፷፱ ዓ. ም. ድረስ በነበረው ጊዜ ግን ፓርቲው ወደ ማፈግፈግ ታክቲክ እንዲዞር ተገደደ ። ምክንያቱም በዚያ ጊዜ አብዮታዊው እንቅስቃሴ ወደ ታች እየወረደ መሄዱን አየን ። የአብዮቱ አካሄድና ታክ ቲኮች የግዴታ ይህንን ሀቅ ልብ ማለት ነበረባቸው ። የትግል አይነቶችና እንዲሁም የድርጅት አይነቶች በዚሁ መሠረት ተለወጡ ። በዱማው ውስጥ መሥራት ፣ ድርጊትንም መፈፀም ፣ በጠቅላላው የፖለቲካ የስራ ማቆም አድማ ፈንታ ግማሽ የኢኮኖሚ የስራ ማቆም አድማ ወይንም እንዲሁ በድርጊቶች በኩል በማድፈጥ ፀጥ ማለት ። በዚያን ጊዜ ፓርቲው መደበቅ ነበረበት ። በዚህኑ ጊዜ አብዮታዊ የብዙሀን ድርጅቶች ደግሞ በባህላዊ ፣ በትምህርታዊ ፣ በህብረት ስራ ፣ በኢንሹራንስና በሌላ ህጋዊ ድርጅቶች ተተኩ ።

ስለሁለተኛውና ስለሶስተኛው የአብዮቱ ደረጃዎች ተመሳሳይ ነገር ማለት ያስፈልጋል ። በእነዚህም ጊዜ የስትራቴጂ እቅዶች ሳይለወጡ ሲቆዩ ታክቲኮች ብዙ ጊዜ ተለውጠዋል ።

ታክቲኮች የወዝአደሩን የትግልና የድርጅት አይነ ቶች ከለውጣቸውና ከውህደታቸው ጋር ያሳያሉ ። እንደ አብዮቱ ውጣ ውረድ ፣ ከፍና ዝቅ ማለት ታክቲኮችም በአንድ በተወሰነ የአብዮቱ ደረጃ ውስጥ ብዙ ጊዜ ሊለዋወጡ ይችላሉ ።

፬. ስትራቴጂክ መሪነት ፡- የአብዮቱ ደጋፊ ሀይ ሎች ፣ ቀጥተኛ ፣ ሀ. ገበሬውና በሀገሪቱ ውስጥ ያሉ በአጠቃላይ መሀል ሰፋሪው የህዝቡ ክፍሎች ፣ ለ. የጎ

ረቤት ሀገሮች ወዝአደር ፡ ሐ. በጥገኛና ቅኝ ሀገሮች
ያለ አብዮታዊ እንቅስቃሴ ፡ መ. የወዝአደሩ የበላይ
ነኝነት ድሎች ፡ የድል ውጤቶች ። ከእነዚህ ውስጥ
ወዝአደሩ ከፊሉን ለጊዜው ሊለቅና ከፍተኛውን የሀ
ይል ሚዛን ግን ይዞ ሊቆይ ይችላል ። ይህንንም የሚያ
ደርገው ሀይለኛ የሆነውን ጠላት ለማግለልና እፎይታ
ለማግኘት ነው ።

ቀጥተኛ ያልሆኑ ፡ ሀ. ሀገሪቱ ውስጥ ባሉ ፡
ወዝአደር ባልሆኑ መደቦች መሀከል ያሉ ቅራኔዎችና
ግጭቶች ። ይህንንም ወዝአደሩ ጠላቶቹን ለማዳከም
ና የራሱንም ደጋፊ (ሪዘርቭ) ሀይሎች ለማጠናከር
ሊጠቀምበት ይችላል ።

ለ. ለወዝአደሩ መንግሥት ክፉ አሳቢ በሆኑ በቡርዧ
መንግስቶች መሀከል ያሉ ቅራኔዎች ግጭቶችና ጦርነቶች ።
(ለምሳሌ የኢምፔሪያሊስት ጦርነት) ይህንንም ወዝ
አደሩ በሚያጠቃበት ጊዜ ወይንም ማፈግፈግ ግዴታ
በሚሆንበት ጊዜ ጠላትን በቅልጥፍና አታሎ በማለፍ
ሊጠቀምበት ይችላል ።

ስለመጀመሪያው ክፍል (ፈርጅ) ደጋፊ ሀይሎች
በሰፊው መናገሩ አስፈላጊ አይደለም ። የሚሰጣቸው
ግምት (ጠቃሚነታቸው) ለሁሉም ሰው ግልጽ ነው ።
ጠቃሚነታቸው ሁልጊዜ ግልጽ ስለማይሆነው ፡ ስለሁ
ለተኛው ክፍል ደጋፊ ሀይሎች ከሆነ ግን ለአብዮቱ
መራመድ አንዳንዴ ከፍተኛ ጥቅም እንዳላቸው መጠ
ቀስ አለበት ። ለምሳሌ በአብዮቱና ከአብዮቱም በኋላ
በንኡስ ከበርቴ ዲሞክራቶችና (ሶሻሊስት አብዮተኞች)
በሊበራል ዘውደኛ ቡርዧዎች (ካዴቶች) መሀከል የነበ
ረው ግጭት የነበረውን ከፍተኛ ጥቅም ማንም ሊክድ



አይችልም ። ገበሬው ከቡርዧው ተጽእኖ ስር እንዲላ
ቀቅ በማድረግ በኩል ይህም ግጭት ያለጥርጥር የራሱን
ድርሻ አዋጥቷል ። ከኢምፔሪያሊስቶች ቡድን ዋና ዋና
ዎቹ በጥቅምቱ አብዮት ጊዜ እጅግ ሀይለኛ በሆነ ጦር
ነት ውስጥ እንደነበሩና ይህም ሀቅ የሰጠውን እጅግ
ከፍተኛ የሆነ ጥቅም መካድ እስከዚህም ምክንያት
አይኖረውም ። ኢምፔሪያሊስቶች እርስ በርሳቸው በሚያ
ካሄዱት ጦርነት ውስጥ ተጠምደው እያለ ገና ወጣት
በሆነው በሶቭየት ስልጣን ላይ ሀይሎቻቸውን ለማተ
ኮር (ለማከማቸት) አልቻሉም ነበር ። በዚህንም ጊዜ
ወዝአደሩ ሀይሎቹን ወደ ማደራጀት ፡ ስልጣንኑ ወደ
ማጠናከሩ ፡ እንዲሁም ኮልቻክንና ዴንኪንን ለመደም
ሰስ ያበቁትን ሁኔታዎች ወደ ማዘጋጀቱ ስራ ለመሰማ
ራት ቻለ ። በኢምፔሪያሊስት ቡድኖች መሀከል ያለው
ቅራኔ በየጊዜው ይበልጥ ከፍተኛ እየሆነ በሄደበትና
በእነሱም መሀከል አዲስ ጦርነት የግዴታ የማይቀር
በሆነበት በአሁኑ ጊዜ የዚህ አይነቱ ደጋፊ ሀይል ለወ
ዝአደሩ ከመቼውም ጊዜ የበለጠ ጥቅም እንደሚኖረው
ለመገመት ይቻላል ።

የስትራቴጂክ መሪነት ተግባር ፡ በአንድ በተሰጠ
የአብዮቱ የእድገት ደረጃ ላይ የአብዮቱን ዋና አላማ
ለማስገኘት እነዚህን ሁሉ ደጋፊ ሀይሎች በደንብ መጠ
ቀም ነው ።

ደጋፊ ሀይሎችን በደንብ መጠቀም ማለት ምን
ማለት ነው?

ይህ ማለት አንዳንድ አስፈላጊ የሆኑትን ሁኔታ
ዎች ማሟላት ማለት ነው ። ከእነዚህም የሚከተሉት
እንደ ዋና ዋናዎቹ ተደርገው መቆጠር አለባቸው ።

መጀመሪያ ፡ የአብዮቱ ደረጃ በዚሁም መጠን አስቸኳይ በሚሆንበት ጊዜ ወሳኝና የጠላት ደካማ ጎን በሆነው ቦታ የአብዮቱን ዋና ሀይሎች ማከማቸት ። ይህም የሚደረገው አብዮቱ የበሰለ ለመሆን በበቃ በት ጊዜ ፡ ማጥቃቱ በተሟላ ሁናቴ ወደፊት በመገስ ገስ ላይ ሳለ ፡ አመፅ በር በሚያንኳኳበት ጊዜ ፡ ደጋፊ ሀይሎችን እስከ ወዝአደሩ ማምጣት ለትግሉ መሳካት ወሳኝ ሁናቴ በሚሆንበት ጊዜ ነው ። ከሚያዝያ እስከ ጥቅምት ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. በነበረው ጊዜ የነበረውን የፓርቲውን ስትራቴጂ እንዲህ ላለው ፡ ደጋፊ ሀይሎችን የመጠቀም ተግባር እንደ ምሳሌ መውሰድ ይቻላል ። በዚያን ጊዜ የጠላት እጅግ ደካማ ነጥቡ ያለጥርጥር ጦርነቱ ነበር ። በዚህ ጥያቄ ላይ ነው ፓርቲው እንደ ዋነኛ አድርጎ በመውሰድ ሰፊውን ህዝብ በወዝአደሩ ግንባር ቀደምትነት አካባቢ ያሰለፈው ። በዚያን ጊዜ የፓርቲው ስትራቴጂ ሀሳቡን በአደባባይ መግለጽና በሰላማዊ ሰልፍ አማካይነት በየአውራ ጎዳናው ለሚከናወኑ ቁርጠኛ ርምጃዎች ማሰልጠን ፡ ከበስተጀርባ በሶቭየቶች አማካይነት ፡ በፊት ለፊት ደግሞ በወታደሮች ኮሚቴ አማካይነት ደጋፊ ሀይሎችን እስከ ግንባር ቀደሙ ድረስ ማምጣት ነበር ። የአብዮቱም ውጤት ደጋፊ ሀይሎችን በትክክል መጠቀም ተችሎ እንደነበረ አሳይቷል ።

ስለአመፅ የማርክስንና የኤንግልስን የታወቁ ቲስሶች በራሱ ቃላት ሌኒን መልሶ ሲጽፍ የአብዮቱን ሀይሎች በስትራቴጂ ስለመጠቀሙ ሁኔታ እንዲህ ይላል ።

፩. ምን ጊዜም ቢሆን በአመፅ አትቀልድ ፡ (አትጫወት) ነገር ግን በምትጀምርበት ጊዜ እስከ



መጨረሻው ድረስ መሄድ እንደሚኖርብህ አጥብቀህ ተገንዘብ ።

፪. እጅግ ብልጫ ያላቸውን ሀይሎች ወሳኝ በሆነ ቦታ ፡ ወሳኝ በሆነ ጊዜ አከማች ። ይህ ካልሆነ የተሻለ ዝግጅትና የተሻለ ድርጅት ለማዘጋጀት ዕድል ያለው ጠላት ተቀናቃኞችን ይደመስሳቸዋል ።

፫. አመፅ አንዴ ከጀመርክ ፍጹም በሆነ ቁርጠኛነት ወደፊት መሄድ አለብህ ። እንዲሁም ምንም ቢሆን ወደኋላ ሳትል የማጥቃትን ሚና ውሰድ ። "በትጥቅ ለተነሳሳ አመፅ ተከላካይነት ሞቱ ነው ።"

፬. ጠላትን እሱ ባላሰበበት ጊዜ በድንገት ለመያዝ መሞከር አለብህ ። ሀይሎቹ የሚበታተኑበትንም ጊዜ ተጠቀም ።

፭. ጥቂት ቢሆንም እንኳን በየቀኑ ለድል መጣር አለብህ ። ጉዳዩ ስለአንድ ከተማም ከሆነ በእያንዳንዱ ሰዓት ለማለት ይቻላል ። የፈለገው ቢመጣ "የሞራል የበላይነትን" ይዘህ መቆየት አለብህ ። (ቅጽ ፳፩ ፡ ገጽ ፫፻፲፱—፫፻፳ ድረስ ይመልከቱ ።)

ሁለተኛ ። ወሳኝ ለሆነው ሞት የሚመረጠው ጊዜና አመፅን ለመጀመር የሚመረጠው ጊዜ ፡ ቀውሱ ከፍተኛው ደረጃ ላይ ከደረሰበት ጊዜ ጋር ፡ ግንባር ቀደሙ እስከመጨረሻው ለመዋጋት ከተዘጋጀበት ጊዜ ጋር ፡ ደጋፊ ሀይሎች ግንባር ቀደሙን ለመደገፍ ከተዘጋጁበትና በጠላት መሀከል ከፍተኛው ተስፋ መቁረጥ ከሚታይበት ጊዜ ጋር እንዲገጥም መደረግ አለበት ።

"ወሳኝ የሆነው ውጊያ ተሟልቶ በስኋል ተብሎ ለመገመት የሚቻለው ፡" ይላል ሌኒን ፤

"፩. የኛ ተቃዋሚ የሆኑ የመደብ ሀይሎች በሙሉ ከአቅማቸው ውጪ በሆነው ትግል እስኪበቃ ድረስ ራሳቸው ከተዳከሙ ፤ ፪. ሁሉም የሚያወላውሉ ፡ የሚያመነቱ ፡ ባንድ ያል ረጉ ፤ መሀል ሰፋሪ ክፍሎች ንኡስ ከበርቴ ፡ ከቡርዧው የተለዩ የሆኑት ንኡስ ከበርቴ ዲሞክራቶች እስኪበቃቸው ድረስ በህዝቡ ፊት ራሳቸውን ካጋለጡ ፡ በተግባር በመክስራ ቸው እስኪበቃቸው ድረስ ራሳቸውን ካቀ ለሉ ፤ ፫. እጅግ ቁርጠኛ ፤ ያለቅጥ ድፍረት የተሞላው አብዮታዊ ድርጊት በቡርዧው ላይ የመውሰድ ልዩ ስሜት በወዝአደሩ መሀከል ፤ በአብዛኛው ዘንድ ከተነሳሳና ያለ ቅጥም ንሮ በሀይል ማደግ ከጀመረ ፤ ያኔ በር ግጥ አብዮቱ በስኋል ። ከላይ የተጠቀሱትን ሁኔታዎች በሙሉ በትክክል መዝነን ከሆነ ጊዜውን በትክክል መርጠን ከሆነ ፡ ያኔ በእር ግጥ የኛ ድል ተረጋግጦአል ።" (ቅጽ ፳፭ ፡ ገጽ ፪፻፷፬ ይመልከቱ ።)

እንዲህ ላለው ስትራቴጂ የጥቅምት የትጥቅ አመፅ የተካሄደበትን ሁናቴ እንደ ሞዴል (ምሳሌ) መውሰድ ይቻላል ።

እንዚህን ሁናቴዎች ማስተዋል አለመቻል "የእን ቅስቃሴን የፍጥነት ልክ መሳት" ወደሚባል አደጋ ያስጠጋል ። ይህም ፓርቲው ከእንቅስቃሴው ጀርባ ሲጎተት ወይንም በጣም ቀድሞት ሲሮጥ ያለው ሁናቴ



መጥራት ነው ። እንዲህ ሲሆን ውጤቱም ውድቀትን "የእንቅስቃሴን የፍጥነት ልክ መሳት" ምሳሌ ፡ ላለው የጊዜ አመራረጥ ትክክል ያልሆነበት አመፅ ለማስነሳት የተወሰኑ ክፍሎች በመስከረም ምሳሌ ፡ ከጓዶቻችን የነበረውን ዲሞክራሲያዊ ጉባኤ[16] በመ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ካደረጉት ሙከራ ሊታይ የሚ ያገ፣ አመፅን ለመጀመር ቻል ነው ። ይህም በሶቭዬቶች ውስጥ ማወላወል ገና ባላቆመበት ጊዜ ፡ በግንባሩ የነበሩት ሰራዊቶች ገና ጣምራ መንገድ ላይ ቆመው ሳለ ፤ ደጋፊ ሀይሎች እስከ ግንባር ቀደሙ እንዲመጡ ባልተደረገበት ጊዜ ነበር ።

ሶስተኛ ፡ ወደ ግቡ በሚወስደው ጎዳና ላይ የፈለ ገው ችግርና ውስብስብ ሁናቴ ቢያጋጥምም የተወሰነ ውንና የተወሰደውን መስመር ሳያዛንፉ መከተል ። ይህም አስፈላጊ የሚሆነው ግንባር ቀደሙ የትግሉ ዋና ግብ እንዳይጠፋበትና ሰፊው ህዝብም ወደ ግቡ በሚጓዝበትና በግንባር ቀደሙ አካባቢ ራሱን በሚያሳ ልፍበት ጊዜ ከጎዳናው ወጥቶ እንዳይባክን ነው ። ይህንን ሁናቴ ማስተዋል አለመቻል መርከበኞች ደህና አድር ገው እንደሚያውቁት "ያሉበትን ቦታ እንደማጣት" ያህል ወደሆነው ከፍተኛ ስህተት ይመራል ። "ያሉበ ትን ቦታ እንደማጣት" ላለ ምሳሌ ልክ ከዲሞክራሲ ያዊ ጉባኤ በኋላ በፓርላማው ውስጥ ለመሳተፍ ውሳኔ ያሳለፈውን የፓርቲያችንን የተሳሳተ አመራር ለመው ሰድ ይቻላል[17] ። ፓርላማው ሀገሪቱን ከሶቭየቶች ጎዳና ወደ ቡርዧ ፓርላማ ለመለወጥ የተደረገ የቡርዧው ጥረት መሆኑንና እንዲህ ባለው አካል ውስጥ የፓርቲው ተሳትፎ ውጤትም "ስልጣን በሙሉ ለሶቭየቶች" በሚል መፈክር ስር አብዮታዊ ትግል ያካሂዱ የነበሩ ትን ሰራተኞችና ገበሬዎች ማደናገርና ሁሉን ነገር ማመ

ሳቀል ሊሆን ይችል እንደነበር ፓርቲው ለአንዳፍታ ስቶት ነበር ። ይህ ስህተት በቦልሼቪኮች ከፓርላማው ለቆ መውጣት ታረመ ።

አራተኛ ፣ ጠላት ጠንካራ ሲሆን ፣ ማፈግፈግ ግዴታ ሲሆን ፣ ጠላታችንን እንድንዋጋው የምንገደድበትን ውጊያ መቀበል ለኛ ጎጂነቱ ግልጽ ሲሆን ፣ በአንድ በተሰጠ የሀይሎች አሰላለፍ በግንባር ቀደሙ ላይ የሚ መጣውን ጥቃት (ምት) በማግለልና የግንባር ቀደሙን ደጋፊዎች ይዞ ለመቆየት ያለው አማራጭ ማፈግፈግ ብቻ ሲሆን ፣ ትክክለኛ ለሆነ ማፈግፈግ ብቁ ለመሆን እንዲችሉ ደጋፊ ሀይሎችን ቀልጣፋ ማድረግ ።

ሌኒን እንዲህ ይላል ።

“አብዮታዊ ፓርቲዎች ትምህርታቸውን መፈፀም አለባቸው ። ማጥቃት ተምረዋል ። አሁን ደግሞ ይህ እውቀት እንዴት ደህና አድ ርጎ ማፈግፈግ በሚያስችል እውቀት መታ ከል እንዳለበት መገንዘብ አለባቸው ። ሁለቱ ንም ማለትም እንዴት ደህና አድርጎ ማጥ ቃትና እንዴትስ አድርጎ ማፈግፈግ እንደሚ ቻል ካልተማሩ በስተቀር ድል የማይቻል መሆ ኑን መገንዘብ አለባቸው ። አብዮታዊ መደብ ይህንን የሚማረው ከራሱ መራር ልምድ ነው ።” (ቅጽ ፳፰ ፣ ገጽ ፩፻፷፯ ይመልከቱ ።)

የዚህ ስትራቴጂ ዓላማ በኋላ ለሚደረገው የማጥ ቃት ዘመቻ ጊዜ ለማትረፍ ፣ ጠላትን ለመበታተንና ሀይሎችን ለማከማቸት ነው ።

የብሬስት የሰላም[18] ውል መፈራረም ለዚህ ስት ራቴጂ ፣ እንደ ሞዴል (ምሳሌ) ሊወሰድ ይቻላል ። ምክ



ንያቱም ፓርቲው ጊዜ እንዲያገኝ ፣ በኢምፔሪያሊስቶች ሰፈር ውስጥ ባለው ግጭት ለመጠቀም ፣ የጠላትን ሀይ ሎች ለመበታተን ፣ የገበሬውን ድጋፍ እንዲያዝ ለመቆ የት ፣ ኮልቻክና ዴንኪንን ለማጥቃት ለሚደረገው ዝግ ጅት ሀይሎችን ለማከማቸት አስቻለው ።

“ለብቻችን ተለይተን የሰላም ውል በማድረጋ ችን በአሁኑ ጊዜ እርስ በርስ ከሚዋጉት ከሁለቱ ም የኢምፔሪያሊስት ቡድኖች የተቻለውን ያህል ራሳችንን ነፃ እናደርጋለን ። በእኛ ላይ ስምምነት ላይ ከመድረስ የሚያግዳቸ ውን ይህን የእነሱን የእርስ በርስ ጠላትነ ትና ጦርነት እንጠቀምበታለን ። ለተወሰነ ጊዜም የሶሻሊስት አብዮቱን ለማራመድና ለማጠናከር እጆቻችን ነፃ ናቸው” ይላል ሌኒን ። (ቅጽ ፳፱ ፣ ገጽ ፩፻፫ ይመልከቱ ።)

ከብሬስት የሰላም ውል በኋላ ሶስት ዓመት ዘግይቶ ሌኒን እንዲህ ይላል ።

“አሁን የመጨረሻው ቂል ሰው እንኳን ‘የብሬስት የሰላም ውል’ እኛን ያጠናከረና የአለምአቀፍ ኢምፔሪያሊዝምን ሀይሎች ግን የበታተነ ስምምነት እንደ ነበረ ለማ የት ይችላል ።” (ቅጽ ፳፯ ፣ ገጽ ፺ ይመል ከቱ ።)

እነኚህ ናቸው ትክክለኛ የስትራቴጂክ መሪነትን የሚያረጋግጡ ዋና ዋና ሁኔታዎች ።

፫. ታክቲካዊ መሪነት ፡- ታክቲካዊ መሪነት የስ ትራቴጂክ መሪነት አንድ ክፍል ፣ የስትራቴጂክ መሪ ነት ተግባሮችና አስፈላጊ ሁኔታዎች የበታች የሆነ

ነው ። የታክቲካዊ መሪነት ተግባር የወዝአደሩን የት-
ግልና የድርጅት አይነቶች በሙሉ በደንብ ማወቅና
እነሱም በትክክል ጥቅም ላይ መዋላቸውን ማረጋገጥ ነው።
ይህም የሚሆነው በተሰጠ የሀይሎች አሰላለፍ ለስትራ
ቴጂክ ድል ለመዘጋጀት የሚያስፈልገውን ከፍተኛውን
ውጤት ለማስገኘት ነው ።

የወዝአደሩን የትግልና የድርጅት ቅርጾች (አይነ
ቶች) በትክክል ጥቅም ላይ ማዋል ማለት ምን ማለት
ነው?

ይህ ማለት አንዳንድ አስፈላጊ ሁናቴዎችን ማሟ
ላት ነው ። ከእነዚህም የሚከተሉት እንደ ዋነኞቹ
መቆጠር አለባቸው ።

መጀመሪያ ፣ በአንድ በተሰጠ የእንቅስቃሴው ውጣ
ውረድ ጊዜ ላሉት ሁናቴዎች ደህና አድርገው የሚስ
ማሙትንና ስለሆነም ሰፊውን ህዝብ ወደ አብዮታዊ
አቋም ማምጣትን ፣ በሚሊዮን የሚቆጠሩትን ወደ አብ
ዮታዊ ግንባር ማምጣትን ፣ በአብዮታዊ ግንባር ማስለ
ፍን አመቺና የተረጋገጠ የሚያደርጉትን የትግልና የድ
ርጅት ቅርጾች በግንባር ቀደም ማስቀመጥ ።

እዚህ ላይ ቁምነገሩ የድሮውን አገዛዝ ለማቆየት
የማይቻልና የእሱ መገልበጥም የግድ የማይቀር መሆ
ኑን ግንባር ቀደሙ መገንዘቡ አይደለም ። ቁምነገሩ
ሰፊው ህዝብ ፣ በሚሊዮን የሚቆጠሩት ህዝቦች ይህ
ነገር የግድ የማይቀር መሆኑን ተረድተው ግንባር
ቀደሙን ለመደገፍ ዝግጁነታቸውን ማሳየታቸው ነው ።
ነገር ግን ሰፊው ህዝብ ይህንን ሊረዳ የሚችለው ከራሱ
ልምድ ነው ። ያለውም ተግባር ሰፊው ህዝብ ከራሱ
ልምድ የድሮውን አገዛዝ መገልበጥ ግዴታነት እንዲገነ



ዘብ ፣ ሰፊው ህዝብ ከልምዱ የአብዮታዊ መፈክሮችን
ትክክለኛነት በቀላሉ እንዲገነዘብ የሚያስችሉትን የት
ግል ዘዴዎችንና የድርጅት ቅርጾችን ማስፋፋት ነው ።

ፓርቲው በጊዜ በዱማ ውስጥ ለመሳተፍ ባይወ
ስን ፣ ሀይሎቹን በዱማ ውስጥ ላለው ስራ ለማከማቸ
ትና ትግሉን በዚህ ስራ መሠረት ላይ ለማዳበር ባይ
ወስን ኖሮ ግንባር ቀደሙ ከሰራተኛው መደብ ይለ
ያይና የሰራተኛው መደብም ከሰፊው ህዝብ ጋር ግን
ኙነት ያጣ ነበር ። ፓርቲው ይህንን ያደረገው ሰፊው
ህዝብ ከራሱ ልምድ የዱማውን ዋጋቢስነት ፣ ካዲቶች
የሰጡት ተስፋዎች ውሸት መሆናቸውን ፣ ከዛር አገዛዝ
ጋር የመቻቻል ድርድር ለማድረግ እንደማይቻል ፣
በሰራተኛው መደብና በገበሬው መሀከል የግዴታ
አጋርነት የማይቀር መሆኑን መረዳት እንዲቀላቸው
ለማድረግ ነበር ። ሰፊው ህዝብ ከዱማው ጊዜ ልምድ
ባይቀስም ኖሮ የካዲቶች መጋለጥና የወዝአደሩ መሪ
ነት የማይቻል ይሆን ነበር ።

"ያለመሳተፍ"[19] ታክቲክ አደጋ የነበረው ግንባር
ቀደሙን በሚሊዮን ከሚቆጠሩት ደጋፊዎች ሊለያየው
በሚችል ስጋት ላይ መጣሉ ነበር ።

ገና በሚያዝያ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ሜንሼቪኮችና ሶሻ
ሊስት አብዮተኞች የጦርነትና የኢምፔሪያሊዝም ደጋፊ
(ጠበቃ) መሆናቸውን ራሳቸውን ባላጋለጡበት ጊዜ ፣
ሰፊው ህዝብ ገና ከራሱ ልምድ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊ
ስት አብዮተኞች ስለሰላም ፣ መሬትና ነፃነት የሚያደር
ጉትን ንግግሮች ሀሰተኛነት ሳይገነዘብ እመጽ እንዲነ
ሳሳ የጣሩትን "የግራ" ኮሚኒስቶች ወዝአደሩ ቢከተል
ኖሮ ፓርቲው ከሰራተኛው መደብ ይገነጠል ነበር ።

የሰራተኛውም መደብ በሰፊው ገበሬና ወታደር መሀከል ተሰሚነቱን ያጣ ነበር ። ሰፊው ህዝብ ክሬንስኪ በነበረበት ጊዜ ይህን ልምድ ባይቀስም ኖሮ ሚንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ተነጥለው ብቸኛ ሊደረጉና የወዝአደሩ የበላይ ገዥነትም ሊሳካ አይችልም ነበር ። ስለዚህ የንኡስ ከበርቴ ፓርቲዎችን ስህተቶች “በትእግስት የመግለጽ” ታክቲክና በሶቭየቶች ውስጥ ግልጽ ትግል ማድረግ ብቻ ነበሩ ትክክለኛ ታክቲኮች ።

“የግራ” ኮሚኒስቶች አደጋ ያሰጋ የነበረው ፓርቲውን ከወዝአደሩ አብዮት መሪነት አንስተው ምንም መቆናጠጫ መሠረት ወደሌላቸው እፍኝ ወደማይሞሉ ፍሬቢስ ሴረኞች ለመለወጥ ማስጋታቸው ነበር ።

> “ድል በግንባር ቀደሙ ብቻ አይገኝም» ይላል ሌኒን “መላው መደብ ፤ ሰፊው ህዝብ ግንባር ቀደሙን ወይ በቀጥታ ለመርዳት ከመሰለፉ በፊት አለዚያም ቢያንስ ቢያንስ ግንባር ቀደሙን ላለመቃወም ፣ ከዚህም ከዚያም ሳይሆን ሀቀኛ ገለልተኛነትን ከማሳየቱ በፊት. . .ግንባር ቀደሙ ብቻውን ከወሳኝ ትግል ውስጥ እንዲገባ መዶል ሞኝነት ብቻ ሳይሆን ወንጀልም ነው ። ለፍቶ አዳሪው ሰፊ ህዝብና በካፒታል የተጨቆኑት እንዲህ አይነቱን አቋም በተጨባጭ መንገድ እንዲይዙ ከተፈለገ ፕሮፓጋንዳና ቅስቀሳ ብቻውን በቂ አይደለም ። ለዚህ ሰፊው ህዝብ የራሱ የፖለቲካ ልምድ ሊኖረው ይገባል ። በአስደናቂ ሀይልና ጥራት በሩሲያ ብቻ ሳይሆን በጀርመንም ጭምር የተረጋገጠው የሁሉም ታላላቅ አብዮቶች መሰረታዊ ህግ እንዲህ



ነው ። ያልሰለጠነውና (አንካልቸርድ) አብዛኛውንም ጊዜ መሀይም የሆነው የሩሲያ ሰፊ ህዝብ ብቻ ሳይሆን ሙሉ በሙሉ የተማረው የጀርመን ሰፊ ህዝብም ከራሱ ስቃይ የተሞላበት ልምድ ፣ የቡርዧውን ፍጹም ፍሬቢስነት ፣ ፍጹም ልፍስፍስነት ፣ ፍጹም ደካማነት ፣ ፍጹም ተለማማጭነት ፣ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ክቡራንን ወራዳነትና ወደ ኮሚኒዝም በቆራጥነት ለመዞር የፍጹም አድሀሪዎቹ የበላይ ገዥነት ያለጥርጥር የግዴታ የማይቀርና (ኮርኒሎቭ በሩሲያ ፣ ካፕና ተከታዮቹ በጀርመን ) ለወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ያለውም አማራጭ መንገድ ይህ ብቻ መሆኑን መገንዘብ ነበረበት” ። (ቅፅ ፳፩ ፣ ገፅ ፪፻፳፰ ይመልከቱ ።)

ሁለተኛ ፣ በአንድ በተሰጠና በተወሰነ ጊዜ በሂደቱ ሰንሰለት ላይ ካሉት መገናኛዎች (ማያያዣዎች) ውስጥ መላውን ሰንሰለት የሚያስጨብጠውንና የስትራቴጂክ ድሉን ለማስገኘት ሁኔታውን ዝግጁ የሚያደርገውን የተወሰነውን መገናኛ (ማያያዣ ሊንክ) መጠቆም ።

እዚህ ላይ ቁምነገሩ ፓርቲውን ከሚገጥሙት ተግባሮች ሁሉ የተወሰነውን አጣዳፊ ተግባር ነጥሎ ማውጣቱ ነው ። የዚህም ተነጥሎ የሚወጣው ተግባር መፈፀም ማእከላዊውን ነጥብ የሚይዝና የሌሎቹንም አጣዳፊ ተግባሮች መሟላት የሚያረጋግጥ ነው ።

የዚህም ቴስስ ጠቃሚነት በሁለት ምሳሌዎች ሊገለጽ ይቻላል ። አንዱ ራቅ ካለ ጊዜ (ፓርቲያችን

በተመሰረተበት ጊዜ) ሌላው ደግሞ ቅርብ ከሆነው
ጊዜ (በአዲሱ የኢኮኖሚ መመሪያ ጊዜ) ነው ። ፓርቲ
ያችን በተቋቋመበት ጊዜ ፥ እጅግ ብዙ የሆኑት የጥናት
ክበቦችና ድርጅቶች ገና ባንድ ላይ ባልተገናኙበት
ጊዜ ፥ አማተርነትና ጠባብ አመለካከት ፓርቲውን ከላይ
እስከታች እንደ ምስጥ ይቦረቡር በነበረበት ጊዜ ፥ የርእ
ዮተ አለም ውዥንብር የፓርቲው ውስጣዊ ኑሮ መለያ
ባህርይ በነበረበት ጊዜ ፥ ፓርቲውን ከገጠሙት የተግ
ባር ሰንሰለቶችና እርስ በርስ ከተቆላለፉት ግንኙነቶች
(ማያያዣዎች) ዋናው ግንኙነትና (ማያያዣ) (ሊንክ)
ዋናው ተግባር የመላው ሩሲያ ሕጋዊ ያልሆነ ጋዜጣ
ማቋቋም ነበር ። (ኢስክራ) ለምን? ምክንያቱም በዚያን
ጊዜ በነበረው ሁኔታ እጅግ ብዙ የነበሩትን የጥናት
ክበቦችና ድርጅቶች ወደ አንድ ሙሉ አካል ለማዋሀድ
የሚችል ፤ የፓርቲውን ጠንካራ ማእከላዊ ስፍራ ለመፍ
ጠር ለርእዮተ አለምና ለታክቲክ የአንድነት ሁኔታዎ
ችን ለማዘጋጀትና በዚያውም ለእውነተኛ ፓርቲ መቋ
ቋም የሚሆኑትን መሰረቶች ለመገንባት የሚቻለው በመ
ላው ሩሲያ ሕጋዊ ባልሆነ ጋዜጣ አማካይነት ብቻ
ነበር ።

ከጦርነት ወደ ኢኮኖሚ መገንባት በነበረው የመ
ሸጋገሪያ ጊዜ ፥ ኢንዱስትሪ በስርአት ማጣት (ዲስራፕ
ሽን) ስር ተይዞ ስራ በመፍታት በሚበሰብስበትና ግብ
ርና ደግሞ በከተማ የሚመረቱ እቃዎች በማጣቱ
በሚቸገርበት ጊዜ ፥ በመንግስት ኢንዱስትሪና በገበሬ
ኢኮኖሚ መሀከል የግንኙነት ሰንሰለት (ማሰሪያ) መቋ
ቋም ለተሳካ የሶሻሊስት መገንባት መሰረታዊ ሁኔታ
በሆነበት ጊዜ ፥ በዚያን ጊዜ በሂደቱ ሰንሰለት ላይ ዋናው
መገናኛ (ማያያዣ) ፥ (ሊንክ) ካሉት ብዙ ተግባሮች
ውስጥ ዋነኛው ተግባር ሆኖ የተገኘው ንግድን ማዳ



በር ነበር ። ለምን? ምክንያቱም በአዲሱ የኢኮኖሚ
መመሪያ (ኤንኢፒ) ሁኔታዎች ስር በኢንዱስትሪና በገበሬ
ኢኮኖሚ መሀከል ያለው መተሳሰሪያ (ቦንድ) በንግድ
አማካይነት ካልሆነ በስተቀር ሊመሰረት አይችልም
ነበር ። ምክንያቱም በአዲሱ ኢኮኖሚ መመሪያ ሁኔታዎች
ስር ምርት ካልተሸጠ በስተቀር ምርት ብቻውን ለኢንዱ
ስትሪ ሞት ነው ። ምክንያቱም ንግድን ከማዳበር የተ
ነሳ በሚመጣ የሺያጭ መስፋፋት አማካይነት ብቻ ነው
ኢንዱስትሪ ሊስፋፋ የሚችለው ። ምክንያቱም አቋማችንን
በንግድ መስክ ካጠናከርን በኋላ ብቻ ፥ ንግድን በቁጥ
ጥራችን ስር ለማዋል ከቻልን በኋላ ፥ ይህንን ግንኙነት
(ሊንክ) አጥብቀን ለመያዝ ከቻልን በኋላ ነው ኢንዱ
ስትሪን ከገበሬው ገበያ ጋር ለማገናኘትና የሶሻሊስት
ኢኮኖሚን መሰረቶች ለመገንባት የሚያስችሉ ሁኔታዎ
ችን ለመፍጠር ፤ ሌሎች አስቸኳይ ተግባሮችን በተሳካ
አኳኋን ለማሟላት ተስፋ የሚኖረን ።

“አብዮታዊና የሶሻሊዝም ተከታይ ወይንም
በአጠቃላይ ኮሚኒስት መሆን ብቻውን አይ
በቃም” ይላል ሌኒን ። “አንድ ሰው በእያን
ዳንዱ የተወሰነ (ልዩ የሆነ) ጊዜ በሰንሰለቱ
ላይ ካሉት መገናኛዎች (ማያያዣዎች) መላ
ውን ሰንሰለት ለመያዝና ወደሚቀጥለው መገ
ናኛ (ማያያዣ) ለመሸጋገር በጥብቅ ለመዘጋ
ጀት እንዲቻል የሚያበቃውን መገናኛ (ማያ
ያዣ) (ሊንክ) ማግኘት አለበት ።”. . .
“በአሁኑ ጊዜ. . . ይህ መገናኛ (ማያያዣ)
(ሊንክ) በተገቢው የመንግስት ቁጥጥር (መመ
ሪያ) ስር የውስጣዊው ንግድ ማንሰራራት
ነው ። ንግድ ፥ ይህንን ነው በድርጊቶች ታሪ

ካዊ ሰንሰለት ላይ ፣ ፲፱፻፷፩—፲፱፻፷፪ በኛ ሶሻሊስት መገንባት መሸጋገሪያ መልኮች (ፎርምስ) ላይ 'ባለን ሀይል ሁሉ መያዝ ያለብን'. . .መገናኛ (ማያያዣ) ።" (ቅጽ ፳፯ ፣ ገፅ ፲፪ ይመልከቱ ።)

ትክክለኛውን ታክቲካዊ መሪነት የሚያረጋግጡ ዋና ዋና ሁኔታዎች እንዲህ ናቸው ።

፮. ጥገናዊነትና አብዮታዊነት ፣ በአብዮታዊ ታክቲኮችና በጥገናዊ ታክቲኮች መሀከል ያለው ልዩነት ምንድን ነው?

አንዳንድ ሰዎች ሌኒኒዝም ጥገናን ይቃወማል ፣ የመቻቻል ድርድርንና (ኮምፕሮማይዝን) በአጠቃላይ ስምምነትን ይቃወማል ብለው ያስባሉ ። ይህ በፍጹም ስህተት ነው ። ቦልሼቪኮች እንደማንኛውም ሰው በተወሰነ አባባል "ጥቃቅኑ ሁሉ እንደሚጠቅም" ፣ በተወሰኑ ሁኔታዎች ስር በአጠቃላይ ጥገናዎችና በተለይም የመቻቻል ድርድሮችና ስምምነቶች አስፈላጊና ጠቃሚም እንደሆኑ ያውቃሉ ።

"በመንግሥታት መሀከል ከሚደረጉትና እጅግ ሞገደኛ ከሆኑ ተራ ጦርነቶች መቶ ጊዜ ይበልጥ አስቸጋሪ ፣ የተራዘመና የተወሳሰበ የሆነውን ኢንተርናሽናል ቡርዧን የመገልበጥ ጦርነት ሲካሄድ ፣ በጠላት መሀከል ያለውን ግጭት ለመጠቀም (ጊዜያዊ ቢሆንም) እንቢ ማለት ፣ ወዳጅ ሊሆኑ ከሚችሉ ጋር ስምምነትንና የመቻቻል ድርድርን (ጊዜያዊ ፣ ያልረጋ ፣ የሚያወላውል ፣ ፍጹም ያልሆነ እንኳን ቢሆንም) እንቢ ማለት ፣ ይህ የመጨረሻ ቂልነት አይደለምን? ይህን ማለት ያልተፈተነና ካሁን በፊት የማይደረስበት የነበረን ተራራ የመውጣት ከባድ ጥረት ሲደረግ አስቀድሞውኑ ጠመዝማዛ በሆነ መስመር አልጓዝም ፣ በወሰድኩት እርምጃ ላይ እንደገና አልመለስም ፣ አንዴ የመረጥኩትን ጎዳና ጥዬ ሌላ አልሞክርም የማለት ያህል አይደለምን?" (ቅጽ ፳፭ ፣ ገጽ ፪፻፲ ይመልከቱ ።)

እንግዲህ ነገሩ ያለው የጥገና ወይንም የመቻቻል ድርድርና የስምምነት ጉዳይ ላይ ሳይሆን ከጥገናና ከስምምነቶች መሀል ህዝቡ ሊያገኝ የሚችለው ጥቅም ላይ እንደሆነ ግልፅ ነው ።

ለጥገና ደጋፊ ጥገና ዋነኛውና ሁሉን የሚይዝ ሲሆን ፣ አብዮታዊ ስራ ግን ለሱ ድንገተኛ የሆነ ፣ እንዲሁ ዝም ብሎ ለወሬ ብቻ የሚሆን መመጻደቂያ ወይንም ማታለያ ነው ። ለዚህ ነው በቡርዧ አገዛዝ ሁኔታዎች ስር ከጥገናዊ ታክቲኮች የሚገኙ ጥገናዎች ያንን አገዛዝ ለማጠናከር ወደሚውል መሳሪያ ፣ አብዮቱን ለመበታተን ወደሚውል መሳሪያነት የግዴታ የሚለወጡት ።

በተቃራኒ ለአብዮታዊ ዋናው ነገር አብዮታዊ ተግባር እንጂ ጥገናዎች አይደሉም ። ለእሱ ጥገናዎች የአብዮቱ ውጤቶች ናቸው ። ለዚህ ነው በቡርዧ አገዛዝ ሁናቴዎች ስር ከአብዮታዊ ታክቲኮች የሚገኙ ጥገናዎች ያው ያንን አገዛዝ ወደሚበታተን መሳሪያ ፣ አብዮቱን ለማጠናከር ወደሚውል መሳሪያ ፣ ለአብዮታዊው እንቅስቃሴ በይበልጥ ማደግ ወደሚሆን ምሽግ የሚለወጡት ።

አብዮታዊ የሆን ጥገናን የሚቀበለው ሕጋዊና
ሕጋዊ ያልሆነን ስራ በሚያገናኝበት ጊዜ እንዲረዳው ፤
ሰፊው ህዝብ ቡርዧውን እንዲገለብጥ ለአብዮታዊ
ዝግጅት ለማብቃት የሚደረገውን ሕጋዊ ያልሆነ ስራን
በጥገና ከለላ ስር ለማፋፋም ሲል ነው ።

በኢምፔሪያሊዝም ሁኔታዎች ስር ከጥገናዎችና
ከስምምነቶች አብዮታዊ ጥቅም የማስገኘት መሰረተ
ነገር (ኤስንስ) ይህ ነው ።

በተቃራኒ ግን የጥገና ደጋፊ ጥገናን የሚቀበለው
ሁሉንም ሕጋዊ ያልሆነ ሥራ ለመተው ፤ የሰፊውን
ሕዝብ አብዮታዊ ዝግጅት ለመቃወምና "በስጦታ"
ጥገናዎች ጥላ ስር ለማረፍ ነው ።

የጥገናዊ ታክቲኮች መሰረተ ነገር ይህ ነው ።

በኢምፔሪያሊዝም ሁኔታዎች ስር ጥገናዎችንና
ስምምነቶችን በሚመለከት ረገድ ያለው አቋም እንዲህ
ነው ።

ይሁን እንጂ ኢምፔሪያሊዝም ከተገለበጠ በኋላ ፤
በወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ስር ሁኔታው ለወጥ ይላል ።
በተወሰኑ ሁኔታዎች ስር ፤ የወዝአደሩ ስልጣን የነገሮችን
አቀማመጥ (አኳኋን) አብዮታዊ በሆነ መንገድ እንደ
ገና የመገንባቱን ጎዳና ለጥቂት ጊዜ ጋብ በማድረግ
ወዝአደር ላልሆኑ መደቦች የጥገናዎችና ኮንሲስዮኖች
ጎዳና ፤ ሌኒን ፤ "የወርቅ አስፈላጊነት" በተሰኘው ጽሑፉ
እንደሚለው "ጥገናዊ ጎዳናን" ለመከተል ይገደድ ይሆ
ናል ፤ ይህም የሚደረገው እነዚህን ወዝአደር ያልሆኑ
መደቦችን ለመበታተን ፤ ለአብዮቱ እፎይታ ለመስጠት ፤
የራስ ሀይሎች እንዲያገግሙ ለማድረግና ሁኔታውን ለአ



ዲስ ማጥቃት ለማዘጋጀት ሲባል ነው ። በተወሰነ አባ
ባል ይህ "ጥገናዊ" ጎዳና መሆኑ አይካድም ። ይሁን
እንጂ እዚህ ላይ መሰረታዊ የሆነ ልዩነት እንዳለ መገ
ንዘብ ያሻል ። ይህም ልዩነት ያለው በዚህ ሁናቴ ጥገ
ናው የሚመነጨው ከወዝአደሩ ስልጣን በመሆኑ ፤ የወ
ዝአደሩን ስልጣን እንደሚያጠናክርና ለእሱም አስፈ
ላጊ የሆነውን እፎይታ እንደሚያስገኝ ፤ አላማውም አብዮ
ቱን ሳይሆን ወዝአደር ያልሆኑ መደቦችን ለመበታ
ተን በመሆኑ ላይ ነው ።

በእንዲህ አይነት ሁኔታዎች ስር ጥገና ወደ ተቃ
ራኒው እንዲህ አድርጎ ይለወጣል ። (ይሸጋገራል ።)

የወዝአደሩ ስልጣን እንዲህ ያለውን መመሪያ
ሊይዝ የቻለበት ምክንያት ቀደም ባለው ጊዜ የአብዮቱ
አመለካከት ታላቅ ስለነበረና ከዚህም የተነሳ የማጥቃት
ታክቲክን በጊዜያዊ የማፈግፈግ ታክቲክ ፤ እንቅስቃሴዎ
ቹን በማጠናከር (ፍላንኪንግ) ታክቲክ ለመተካት ፤
ለማፈግፈግ የሚያስችል ሰፊ የሆነ ቦታ ይሰጥ ስለነ
በረ ነው ።

በዚህ ሁናቴ ቀደም ብሎ በነበረው ጊዜ በቡርዧ
ው አገዛዝ ስር ጥገናዎች የአብዮት ውጤት ነበሩ ።
አሁን በወዝአደሩ የበላይ ገዥነት ስር የጥገናዎች ምንጭ
የወዝአደሩ አብዮታዊ ድሎች ፤ እነዚህን ድሎች የሚይ
ዝና በወዝአደሩ እጆች የተጠራቀሙ ደጋፊዎች (ድጋ
ፎች) ናቸው ።

"የጥገናንና የአብዮቱን ግንኙነት በትክክል
የገለፀው ማርክሲዝም ብቻ ነው" ይላል
ሌኒን ። "ማርክስ ይህን ግንኙነት ሊያይ የቻ
ለው ከአንዱ ገጽ ብቻ ነበር ፤ ማለትም የመጀመ

ሪያውን ከሚቀድሙ ፣ በአንድ ሀገር ውስጥ
ብቻ ቢሆንም ከሞላ ጎደል ዘላቂና ቋሚ
ከሆነ የወዝአደሩ ድል ሁኔታዎች ስር ያለ
ውን ነበር ። በእነዚህ ሁኔታዎች ስር ተገቢ
የሆነው ግንኙነት መሰረት የሚከተለው
ነው ። ጥገናዎች የወዝአደሩ አብዮታዊ የመደብ
ትግል ውጤቶች ናቸው ።. . .ከወዝአደሩ ድል
በኋላ በአንድ ሀገር ብቻ ቢሆንም እንኳን
በጥገናና በአብዮት ግንኙነት መሀከል አንድ
አዲስ ነገር ይገባል ። በመሰረተ ሃሳቡ ልክ
እንደበፊቱ ነው ። ይሁን እንጂ በቅርጽ ላይ
ማርክስ ቀደም ብሎ ሊያየው ይችል ያልነ
በረ ለውጥ ተደርጎአል ። ሆኖም ይህን ለውጥ
በደንብ ለመረዳት የሚቻለው በማርክሲ
ዝም ፍልስፍናና ፖለቲካ መሰረት ላይ
ነው ።. . .ከድሉ በኋላ ፣ (በአለም ፖለቲካ
ደረጃ ገና "የአብዮት ውጤት" ሆነው ሳለ)
ድሉ ለተገኘበት ሀገር ከፍተኛ የሆነ ጥረት
እየተደረገ ፣ ለዚህ ወይንም ለዚያ የመሸጋገ
ሪያ ጊዜ አብዮታዊ ክንውን በቂ የሆነ አቅም
አለመኖሩ ግልጽ ሲሆን ጥገና አስፈላጊና
ትክክለኛ የሆነ እፎይታ ማግኛ ነው ። ድል
ተጠባባቂ የሆነ ሀይል' ስለሚፈጥር የግ
ዴታ ማፈግፈግ በሚኖርበት ጊዜ እንኳን
በማቴሪያልም ሆነ በሞራል ጠንክሮ ለመቆ
የት ይቻላል ።"

(ቅፅ ፳፯ ፣ ገፅ ፻፬—፻፭ ይመልከቱ ።)



## ፰. ፓርቲው

ከአብዮታዊው ጊዜ በፊት ፣ ከሞላ ጎደል ሰላማዊ
ዕድገት በነበረበት ጊዜ ፣ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል
ፓርቲዎች በሠራተኛው መደብ እንቅስቃሴ ውስጥ
የበላይነት ሀይል በነበራቸውና ፓርላማዊ የትግል ዓይ
ነቶችም እንደ ዋነኛ ዓይነት ተደርገው ይቆጠሩ በነ
በረበት ጊዜ ፣— በእነዚህ ሁኔታዎች ሥር ፓርቲው በኋላ
በግልጽ አብዮታዊ ግጭቶች ጊዜ ያገኘውን ታላ
ቅና ወሳኝ የሆነውን ከፍተኛ ግምት ሊያገኝም ሆነ
ሊኖረውም አይችልም ነበር ።

ሁለተኛው ኢንተርናሽናልን በመደገፍና በኢንተር
ናሽናሉ ላይ የሚቀርበውንም ክስ (አታክ) በመቃወም
ካውትስኪ ሲመልስ የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲ
ዎች የሰላም እንጂ የጦርነት መሣሪያዎች አይደ
ሉም ፣ በዚህም ምክንያት በጦርነቱም ጊዜ በወ
ዝአደሩ አብዮታዊ ድርጊት ጊዜ ፣ ምንም ዓይነት
ጠቃሚ እርምጃ ለመውሰድ አቅም አልነበራቸውም
ነበር ይላል ። ይህ እርግጥ ነው ። ግን ምን ማለት ነው?
ይህ ማለት የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች
ለወዝአደሩ አብዮታዊ ትግል የሚስማሙ አይደሉም ።
ሠራተኞችን ወደ ሥልጣን የሚመሩ የወዝአደሩ ታጋይ
(ሚሊታንት) ፓርቲዎች ሳይሆኑ ለፓርላማዊ ምርጫ
ዎችና ለፓርላማዊ ትግል የሚሆኑ የምርጫ መኪና
ዎች ናቸው ማለት ነው ። ከዚህም በላይ የሁለተኛው
ኢንተርናሽናል አድርባዮች የበላይነት እያገኙ በመሄድ
ላይ በነበሩበት ጊዜ የወዝአደሩ ዋና የፖለቲካ ድርጅት
ፓርቲው ሳይሆን ፓርላማዊ ቡድን እንደነበረ ይገል
ጻል ። ፓርቲው በዚያን ጊዜ የፓርላማዊ ቡድን ተቀጽ
ላና ተከታይ እንደነበረ የታወቀ ነገር ነው ። እንደዚህ

ባሉ ሁኔታዎች ሥርና እንደዚህ ያለ ፓርቲ ቁንጮ ላይ ቁጭ ብሎ ወዝአደሩን ለአብዮቱ የማዘጋጀት ጥያቄ ሊኖር እንደማይችል እስከዚህም ማረጋገጫ አያሻውም ።

ከአዲሱ ጊዜ መምጣት (ጎህ መቅደድ) ጋር ሁኔታዎች በሥር ነቀል አኳኋን ተለውጠዋል ። አዲሱ ጊዜ የግልጽ የመደብ ግጭቶች ጊዜ ፤ አብዮታዊ ድርጊት በወዝአደሩ የሚፈጸምበት ጊዜ ፤ የወዝአደሩ አብዮት ጊዜ፤ ለኢምፔሪያሊዝም መገልበጥና ሥልጣንንም ለወዝአደሩ ለማስያዝ ሀይሎችን በቀጥታ መሰብሰብ የተፋፋመበት ጊዜ ነበር ። በዚህ ጊዜ ሁሉንም የፓርቲውን ሥራ በአዲስ አብዮታዊ መስመር ላይ እንደገና የማደራጀት አዲስ ተግባር ወዝአደሩን ገጠመው ። ይህም ለሥልጣን በሚደረግ አብዮታዊ ትግል መንፈስ ሠራተኞችን ማስተማር ፤ ደጋፊ ሀይሎችን ማዘጋጀትና ማንቀሳቀስ ፤ ከጎረቤት ሀገሮች ወዝአደር ጋር አጋርነት መፍጠር ፤ በቅኝና ጥገኛ ሀገሮች ካሉ የነፃነት እንቅስቃሴዎች ጋር የጠበቀ ግንኙነት መፍጠር . . .ወዘተ ነበር ። እነዚህ አዲስ ተግባሮች በሰላማዊና ፓርላማዊ ሁኔታዎች ስር ባደጉበት በድሮዎቹ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲዎች ይከናወናሉ ብሎ ማሰብ ራስን ቀቢፀ—ተስፋ ውስጥ ፤ የማይቀር መሸነፍ ውስጥ መክተት ነው ። እንዲህ ያሉትን ተግባሮች ማካሄድ ትከሻው ላይ ወድቆ እያለ ወዝአደሩ በድሮዎቹ ፓርቲዎች መሪነት ሥር ቢቀር ሙሉ በሙሉ ትጥቅ የሌለው ይሆን ነበር ። ወዝአደሩ እንዲህ ላለው ሁናቴ ፈቃደኛ እንደማይሆን እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ።

ስለሆነም አዲስ ፓርቲ ፣ ታጋይ (ሚሊታንት) ፓርቲ ፣ አብዮታዊ የሆነ ፓርቲ ፣ ወዝአደሮችን ለሥልጣን ትግል ለመምራት ደፋር የሆነ ፓርቲ ፣ አብዮታዊ



በሆነ ሁኔታ ውስብስብ ከሆኑ ሁኔታዎች ውስጥ ያለበትን ቦታና አቅጣጫ በመፈለግ ረገድ በቂ ልምድ ያለውና እግቡ ጎዳና ላይ ተቀብረው ካሉት ጋሬጣዎች ወዲያ ወዲህ ብሎ ተሽሎክልኮ ለማለፍ በቂ ችሎታ ያለው ግትር ያልሆነ ፓርቲ አስፈላጊ ሆነ ።

ያለእንደዚህ ያለ ፓርቲ ኢምፔሪያሊዝምን ለማስወገድና የወዝአደሩን የበላይ ገዥነት ለመመሥረት ቀርቶ ስለዚሁ ማሰቡ እንኳን ዋጋቢስ ነው ።

ይህ አዲስ ፓርቲ የሌኒኒዝም ፓርቲ ነው ።

የዚህ አዲስ ፓርቲ የተለዩ ባህርይዎች ምንድን ናቸው?

፩. <u>ፓርቲው የሠራተኛው መደብ የተራመደ ልዩ ክፍል (አድቫንስድ ድታችመንት) ስለመሆኑ ፤</u> ፓርቲው ከሁሉ አስቀድሞ የሠራተኛው መደብ የተራመደ ልዩ ክፍል መሆን አለበት ። ፓርቲው ማንኛቹንም የሠራተኛውን መደብ እጅግ ጥሩ የሆኑ ክፍሎች (ኤሌመንትስ) ፤ ልምዳቸውን ፤ አብዮታዊ መንፈሳቸውን ፤ ለወዝአደሩ አላማ ራስን አሳልፎ እስከመስጠት ያላቸውን ታማኝነት ማዋሀድ አለበት ። ነገር ግን በእርግጥም የተራመደና የተለየ ክፍል ለመሆን ፓርቲው በአብዮታዊ ቲዎሪ ፣ በእንቅስቃሴው ሕግጋት ዕውቀት ፣ በአብዮቱ ሕግጋት ዕውቀት ፣ መታጠቅ አለበት ። ያለእዚህ የወዝአደሩን ትግል ለመምራት ፣ ወዝአደሩን ለመምራት አይችልም ። ፓርቲው ሰፊው የሠራተኛው መደብ ምን እንደሚሰማውና ምን እንደሚያስብ በመመዝገብ ብቻ ራሱን ከወሰነ ፣ ከግብታዊው እንቅስቃሴ ጀርባ ከተጎተተ ፣ የግብታዊውን እንቅስቃሴ የፖለቲካ ግድየለሽነትና የመወ

ዘፍ ስሜት ሊያስወግድ ካልቻለ፣ ከጊዜያዊ የወዝአደሩ ጥቅሞች በላይ ከፍ ሊል ካልቻለ፣ የወዝአደሩን የመደብ ጥቅሞች ወደ መረዳት ደረጃ ሰፊውን ሕዝብ ከፍ ለማድረግ ካልቻለ፣ እውነተኛ ፓርቲ ሊሆን አይችልም። ፓርቲው በሠራተኛው መደብ ግንባር መቆም አለበት። ከሠራተኛው መደብ የተለየ አርቆ ማየት አለበት። ወዝአደሩን መምራት አለበት እንጂ ከግብታዊው እንቅስቃሴ ጀርባ መንተት የለበትም። «ጭራነትን» የሚሰብኩት የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች ወዝአደሩን በቡርዧው እጆች ውስጥ እንዳለ መሣሪያ የሚኮንኑ የቡርዧ መመሪያ አስፈጻሚ መሣሪያዎች ናቸው። የወዝአደሩን የተራመደ ልዩ ክፍል አቋም የሚይዝና የወዝአደሩን የመደብ ጥቅሞች ወደ መረዳት ደረጃ ሰፊውን ሕዝብ ከፍ ለማድረግ የሚችል ፓርቲ፤ እንዲህ አይነቱ ፓርቲ ብቻ ነው፤ የሠራተኛውን መደብ ከሙያ ማህበርነት ጎዳና ለውጠ ወደ ነፃ የፖለቲካ ሀይል የሚያዞረው። ፓርቲው የሠራተኛው መደብ የፖለቲካ መሪ ነው።

ቀደም ብዬ ስለሠራተኛው መደብ ትግል ችግሮች፣ ስለስትራቴጂና ታክቲኮች፣ ስለደጋፊ ሀይሎችና አሰላለፍ፣ ስለማጥቃትና ማፈግፈግ ተናግሬአለሁ። እነዚህ ሁኔታዎች ውስብስብነታቸው ከጦርነት ሁኔታዎች ቢበልጥ እንጂ አያንስም። በእነዚህ ሁኔታዎች ሥር ማነው አጥርቶ ሊያይ የሚችለው? በሚሊዮን ለሚቆጠሩ ወዝአደሮች ትክክለኛውን አመራር የሚሰጥ ማነው? በጦርነት ላይ ያለ ማንኛውም ሠራዊት የመሸነፍ ዕዋ ለመቅመስ ካልፈለገ በስተቀር ልምድ ያላቸውን የጠቅላይ ጦር መምሪያ አባሎች ልምድ ሊያስወግድ አይችልም። ታዲያ ወዝአደሩ የሞትና የሽረት ጠላቶቹ በሆኑት ከመቦጫጨቅ ራሱን ለማዳን ከፈለገ እንደዚህ



ያሉትን የጠቅላይ መምሪያ አባሎቹን ከግዳጃቸው ማስወገድ እንደሚሳነው ግልጽ አይደለም? ታዲያ ይህ ጠቅላይ መምሪያ የት ነው ያለው? የወዝአደሩ አብዮታዊ ፓርቲ ብቻ ነው እንደዚህ እንደ ጠቅላይ ጦር መምሪያ አባሎች ሆኖ ሊያገለግል የሚችለው። አብዮታዊ ፓርቲ የሌለው የሠራተኛ መደብ ካለ ጠቅላይ መምሪያ የቀረ ሠራዊት ነው።

## ፓርቲው የወዝአደሩ ጠቅላይ መምሪያ ነው ።

ፓርቲው የተራመደ ልዩ ክፍል ብቻ ሊሆን አይችልም። በተጨማሪም የመደቡ የተለየ ክፍል፤ ከጠቅላላ የሕልውናው ድሮች ጋር በቅርብ የተሳሰረ የመደቡ አካል ነው። በተራመደው ልዩ ክፍልና በተቀረው የሠራተኛ መደብ መሀከል፣ በፓርቲ አባሎችና የፓርቲው አባል ባልሆኑት መሀከል ያለው ልዩነት መደቦች ራሳቸው እስኪጠፉ ድረስ አይጠፋም። የወዝአደሩ መደብ አባሎች የሌላ መደብ አባሎች በነበሩ ሰዎች እየተሞላ እስከሄደ ድረስ፣ ጠቅላላው የሠራተኛው መደብ የተራመደው ልዩ ክፍል ደረጃ ድረስ ከፍ ለማለት እስካልቻለ ድረስ ልዩነቱ ይኖራል።

ይህ ልዩነት በጣም ሰፊ ወደሆን መለያየት ካደገ፤ ፓርቲው በራሱ ላይ በማትኮር የፓርቲው አባል ካልሆነው ሰፊ ሕዝብ ከተገነጠለ ፓርቲ መሆኑ ያበቃል። የፓርቲው አባል ካልሆነው ከሰፊው ሕዝብ ጋር ካልተያያዘ፣ በፓርቲውና የፓርቲው አባል ካልሆነ ሰፊ ሕዝብ ጋር ማስተሣሰሪያ ሀይል ከሌለ፣ ይህም ሕዝብ መሪነቱን ካልተቀበለ፣ ፓርቲው በሰፊው ሕዝብ ዘንድ የሞራልና የፖለቲካ ጥሩ ተሰሚነት (እምነት) ከሌለው ፓርቲው መደቡን ሊመራ አይችልም።

በቅርብ ጊዜ ከሠራተኞች ውስጥ ሁለት መቶ ሺህ አዲስ አባሎች ፓርቲያችን ውስጥ እንዲገቡ ተደርጎ ነበር ። ታዲያ የዚህ ጉዳይ በጣም ተደናቂው ነገር እነዚህ ሰዎች ይህን ያህልም በራሳቸው ጥረት ፓርቲው ውስጥ አለመግባታቸው ነው ። ወደዚያ የተላኩት በተቀሩት ፣ የፓርቲ አባል ባልሆኑ ሠራተኞች ፤ አዲስ አባሎችን በማስገባት ቀልጣፋውን ድርሻ በያዙና ያለ እነሱም ተሳትፎ ምንም አዲስ አባል መቀበል በማይቻለው በሠራተኞች ነበር ። ይህ ሀቅ የሚያሳየው የፓርቲው አባል ያልሆኑ ሰፊ ሠራተኞች ፓርቲያችንን እንደ ራሳቸው ፓርቲ በጣም እንደሚወዱት ፣ እንደሚያፈቅሩት ፣ በመስፋፋቱና በመጠናከሩ እጅግ ከፍተኛ ፍላጎት እንዳላቸውና በገዛ ፈቃዳቸው የወደፊት ዕድላቸውን ለእሱ መሪነት አምነው እንደሚሰጡ ነው ። ፓርቲውን የፓርቲው አባል ካልሆነው ሰፊ ሕዝብ ጋር ከሚያገናኙ ካለእነዚህ በእጅ የማይዳሰሱ የሞራል ክሮች በስተቀር ፓርቲው የመደቡ ወሳኝ ሀይል ሊሆን አይችልም ነበር ።

## ፓርቲው ሊገነጠል የማይቻል የሠራተኛው መደብ አካል ነው ።

“እኛ” ይላል ሌኒን “የመደብ ፓርቲ ነን ። ስለሆነም መላውን መደብ ሊያጠቃልል ምንም ያህል የማይቀረው ክፍል ፣ (በጦርነት ፣ በእርስ በርስ ጦርነት ጊዜ መላው መደብ) በኛ ፓርቲ መሪነት ስር መካሄድ ፣ በተቻለ መጠን የኛን ፓርቲ አጥብቆ መያዝ አለበት ። ነገር ግን በካፒታሊዝም ስር መላውን መደብ ሊያጠቃልል ምንም ያህል የማይቀረውን መደብ ወይንም ደግሞ መደቡ በሞላ የተራመደው ልዩ ክፍል ወደሆነው ወደ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ደረጃ ንቃቱንና ድርጊቱን ከፍ ሊያደርግ ይችላል ብሎ ማሰብ ማኒሎቪዝምና[20] ‘ጭራነት’ ይሆናል ። እስካሁን ድረስ ማንም ህሊና ያለው ሶሻል ዲሞክራት የሙያ ማህበር ድርጅቶች እንኳን (ወደኋላ የቀረውና ያልዳበረው ክፍል ይበልጥ ሊገባውና ሊረዳው የሚችለው) በካፒታሊዝም ሥር መላውን የሠራተኛ መደብ ወይንም ደግሞ ወደዚያ የሚጠጋውን ያህል ለማቀፍ እንዳልቻሉ ተጠራጥሮ አያውቅም ። በተራመደው ልዩ ክፍልና ወደእሱ በሚሳበው በመላው ሰፊ ሕዝብ መሀከል ያለውን ልዩነት መርሳት ፣ በየጊዜው ይበልጥ ሰፊ ያለውን ክፍል እጅግ ወደተራመደው ደረጃ ከፍ ለማድረግ የተራመደው ልዩ ክፍል የሚያደርገውን የቀን ተቀን ተግባር መርሳት ፣ ራስን ማታለል ፣ እጅግ ብዙ በሆነው ተግባራችን ላይ የራስን ዓይን መጨፈንና እነዚህን ተግባሮች ጠባብ ማድረግ ማለት ነው ።” (ቅጽ ፯ ፡ ገጽ ፪፻፮—፪፻፯)

፱. ፓርቲው የተደራጀ የሠራተኛው መደብ ልዩ ክፍል ስለመሆኑ ፣ ፓርቲው የሠራተኛው መደብ የተራመደ ልዩ ክፍል ብቻ አይደለም ። የመደቡን ትግል በእውነት ለመምራት ከፈለገ በተጨማሪ የመደቡ የተደራጀ ልዩ ክፍል መሆን አለበት ። በካፒታሊዝም ሁኔታዎች ስር የፓርቲው ተግባሮች እጅግ ብዙና በጣምም የተለያዩ ናቸው ። ፓርቲው ያለቅጥ አስቸጋሪ በሆኑ የውስጥና የውጪ እድገት ሁኔታዎች ስር የወዝአደሩን ትግል መምራት አለበት ። ሁኔታው ማጥቃት ሲጠይቅ ፓርቲው ወዝአደሩን ለማጥቃት ተግባር መምራት አለበት ። ሁኔታው ማፈግፈግን በሚጠይቅበት ጊዜ ከሀይለኛ ጠላት በትር ስር እንዲያመልጥ ወዝአደሩን

መምራት አለበት ። በሚሊዮን የሚቆጠሩትን ያልተደራጁ ከፓርቲ ውጪ የሆኑ ሠራተኞችን በትግሉ ውስጥ በስርዓትና በዲስፕሊን መንፈስ ፣ በድርጅትና ችግርን በመቋቋም መንፈስ ማጥመቅ (ማነፅ) አለበት ። ነገር ግን ፓርቲው እነዚህን ተግባሮች ሊያሟላ የሚችለው ራሱ ዲስፕሊንና ድርጅት በተጨባጭ መንገድ የሚታዩበት አካል ሲሆን ፣ እሱ ራሱ የወዝአደሩ የተደራጀ ልዩ ክፍል ሲሆን ብቻ ነው ። ያለእነዚህ ሁኔታዎች ፓርቲው ሰፊውን ወዝአደር በእርግጥ የመምራቱ ጥያቄ ሊነሳ አይችልም ።

### ፓርቲው የተደራጀው መደብ የሠራተኛው ልዩ ክፍል ስለ መሆኑ

የፓርቲው እንደ አንድ የተደራጀ ሙሉ አካል የመሆኑ ፅንሰ ሃሳብ በፓርቲያችን ሕግጋት የመጀመሪያው ክፍል በሆነው በታወቀው በሌኒን አጠቃላይ አባባል ውስጥ ይገኛል ። በዚህም ውስጥ ፓርቲው የድርጅቶች ጠቅላላ ድምር ተደርጎ ተቆጥሯል ። የፓርቲው አባል ከፓርቲው ድርጅቶች ውስጥ የአንደኛው አባል ተደርጎ ተቆጥሯል ። ገና ከ፲፱፻፫ ዓ. ም. ጀምሮ ይህንን አጠቃላይ አባባል ይቃወሙ የነበሩት ሜንሼቢኮች በምትኩ አቅርበውት የነበረው የፓርቲ አባልነት «መጠሪያ» በዚህ ወይንም በዚያ ረገድ ፓርቲውን ለደገፈ ፣ ነገር ግን በማንኛውም በፓርቲው ድርጅት ውስጥ ላልገባና ሊገባም ላልፈለገ ለማንኛውም «ፕሮፌሰርና» የሁለተኛ ደረጃ ተማሪ ፣ «ለማንኛውም» አድማ አድራጊና» «ደጋፊ» (ሲመፓታይዘር) በመስጠት «ሥርዓት» ፣ በፓርቲው ውስጥ ራስን አጭቶ በማስገባት «ሥርዓት» ለመተካት ሃሳብ አቅርበው ነበር ። ይህ እንግዳ የሆነ «ሥርዓት» በፓርቲያችን ውስጥ ስር ቢሰድ ኖሮ የግ



ዶ፡ታ ፓርቲያችን በፕሮፌሰሮች ፣ በሁለተኛ ደረጃ ተማሪዎች ወደ መጥለቅለቁና ወደ ልቅ ፣ ቅርፀቢስ ፣ የተበታተነ «መዋቅር» ዝቅ ይል ነበር ። ከዚህም የተነሣ «በደጋፊዎች» ባህር ውስጥ ሰምጦ ራሱን በማጣት ፣ በፓርቲውና በመደቡ መሀከል ያለውን መስመር ወደ ማጥፋትና ያልተደራጀውን ሰፊ ሕዝብ የተራመደው ልዩ ክፍል ወደሆነው (ፓርቲው ፣) ደረጃ ከፍ የማድረጉን ተግባር ወደማናጋት ይመራ እንደነበረ እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ። በአብዮታችን ጉዞ ውስጥ እንዲህ ባለ አድርባይ «ሥርዓት» ስር ፓርቲያችን የአደራጅነቱን ሚና ለሚማላት አይችል እንደ ነበረ መግለጹ አስፈላጊ አይደለም ።

«ከጓድ ማርቶቭ አቋም አንፃር ሲታይ» ይላል ሌኒን «የፓርቲው ድንበር መለያ ምንም ወሰን የሌለው ሆኖ ይቀራል ። ምክንያቱም ማንኛውም አድማ አድራጊ ራሱን 'የፓርቲው አባል አድርጎ ሊያውጅ' ይችላል ። የዚህ ግልጽ ያለመሆን ጥቅሙ ምንድን ነው?' 'የመጠሪያው' በሰፊው መሰራጨት ጎጂነቱ ድርጅቱን የሚበታትን ሃሳብ ማምጣቱ ነው ፣ የመደብና የፓርቲ መወነዣበር» (ቅጽ ፳፯ ፣ ገጽ ፪፻፲፩ ይመልከቱ ።)

ፓርቲው የፓርቲው ድርጅቶች ጠቅላላ ድምር ብቻም አይደለም ። ፓርቲው በተጨማሪ የእነዚህ ድርጅቶች ነጠላ ሥርዓት ፣ የበላይና የበታች መሪ አካሎች ያሉት ፣ ንዑሳን ለብዙሀን የሚታዘዙበት ፣ ተግባራዊ ውሳኔዎች በሁሉም ፓርቲ አባሎች ላይ መጽናት ያለበት ፣ በአንድ ሙሉ አካል ስር የድርጅቶቹ ታይታይ (ፎርማል) መዋሀድ ነው ። ያለእነዚህ ሁኔታዎች ፓርቲው

ለሠራተኛው መደብ ትግል ሥርዓት ያለው የተደራጀ የመሪነት ተግባሩን ለማካሄድ የሚችል አንድ የተሟላ ድርጅት ሊሆን አይችልም ።

«ድሮ» ይላል ሌኒን ፣ «ፓርቲያችን በታይታይ (ፎርማል) የተደራጀ አንድ ሙሉ አካል ሳይሆን ፣ የተለያዩ ቡድኖች ድምር ብቻ ነበር ። ይህም ስለሆነ በእነዚህ ቡድኖች መሀከል ከርእዮተ ዓለም ተፅእኖ በስተቀር ሌላ ዓይነት ግንኙነቶች ሊኖሩ አልቻሉም ነበር ። አሁን የተደራጀ ፓርቲ ሆነናል ፣ ይህም የሥልጣንን መቋቋም ፣ የሃሳቦች ሀይል ወደ ሥልጣን ሀይል መለወጣቸውን ፣ የታችኛው የፓርቲው አካል ለላይኛው የፓርቲ አካል ታዛዥ መሆኑን ያስመለክታል ።» (ቅጽ ፲ ፣ ገጽ ፪፻፲፩ ይመልከቱ ።)

ንኡሳን ለብዙሀን የመታዘዘ መርህ ፣ የፓርቲውን ሥራ ከማእከላዊ ነጥብ የመምራቱ መርህ ፣ ወላዋይ የሆኑት ክፍሎች አልፎ አልፎ «ቢሮክራሲ» «ፎርማሊዝም» . . .ወዘተ. የሚሉ ክሶች እንዲያነሱ ምክንያት ይሆናቸዋል ። እነዚህ መርሆች በተግባር ላይ ባይውሉ ኖሮ የፓርቲው እንደ አንድ ሙሉ አካል ሆኖ ሥርዓት ያለው ሥራ መሥራትና የሠራተኛውን መደብ መምራት ፣ የማይቻል ይሆን እንደነበረ እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ። በድርጅታዊ ጥያቄዎች ላይ ሌኒኒዝም የእነዚህ መርሆች ያለማወላወል ተግባር ላይ መዋል ማለት ነው ።

በእነዚህ መርሆች ላይ የሚያረገውን ውጊያ ሌኒን «የሩሲያ ኒሂሊዝም» «መሳፍንታዊ አናርኪዝም» ብሎ በመጥራት መሳለቂያ ሊሆንና ተጠርጎ ወዲያ መጣል የሚገባው ነው ይለዋል ።



<u>አንድ እርምጃ ወደፊት</u> በሚለው መጽሐፉ ውስ
ስለእነዚህ ወላዋይ ክፍሎች ሌኒን የሚለው እነሆ ፤

«ይህ መሳፍንታዊ አናርኪዝም በተለይ የሩሲያ ኒሂሊስት ልዩ ባህርይ ነው ። የፓርቲውን ድርጅት እጅግ ግዙፍና አስፈሪ እንደሆነ «ፋብሪካ» አድርጎ ያየዋል ። አነስተኛው ክፍል ለመላው አካል ፣ ንኡሱ ለብዙሀኑ ያለውን ተገዢነት እንደ «ገባርነት». . . ይቆጥረዋል ። ከማእከላዊው አመራር ስር የሚመጣ የሥራ መከፋፈል ሰዎች ወደ መሣሪያነት ተለወጡ የሚል አሳዛኝና አስቂኝ የሆነ ጩኸትን ይቀሰቅስበታል ። የፓርቲው ድርጅታዊ ሕግጋት መጠቀስ ፣ ሕግን እንዳለ ወዲያ ለመጣል ይቻላል የሚል ንቀት የተሞላበት የጥላቻና የማንቋሸሽ. . .አባባልን ያስከትላል። ስለዚህ የተከበረ ቢሮክራሲ ያለው ሮሮ የማእከላዊው አካል አባሎች ከሆኑት ጋር ላለው አለመጣጣም ከለላ ፣ መጋረጃ ብቻ እንደሆነ ግልጽ ይመስለኛል ።. . . አንተ ቢሮክራት ነህ ፣ ምክንያቱም በጉባኤው የተመረጥከው የኔ ፍላጎት ሆኖ አይደለም ። እንዲያውም በተቃራኒ ፍላጎቴ ሳይሆን ነው ። ፎርማሊስት ነህ ፣ ምክንያቱም በጉባኤው ፎርማል ውሳኔ ላይ እንጂ እኔ በፈቀድኩት ላይ አትተማመንም ። እንዲሁ ዝም ብለህ በአጠቃላይ መካኒካዊ በሆነ መንገድ ድርጊትህን ታከናውናለህ ፣ ምክንያቱም በፓርቲው ጉባኤ ያሉትን «መካኒካዊ የሆኑ» ብዙሀን ትማጠናለህ እንጂ የኔ ፍላጎት ድጋፍ እንዲያገኝ አታስብም።ተቀናቃኝ የሌለብህ ቆራጭ ፈላጭ ነህ ፣ ምክንያቱም ሥል

ጣንኑ ለቀድሞው ቡድን[21] ማስረከብን እንበ.
ትላለህ።(ቅጽ ፩ ፡ ገጽ ፫፻፲ ፡ ፪፻፹፮ ይመልከቱ።)

፫. ፓርቲው የወዝአደሩ የመደብ ድርጅት ከፍ
ተኛው ዓይነት ስለመሆኑ ። ፓርቲው የሠራተኛው
መደብ የተደራጀ ልዩ ክፍል ነው ። ይሁን እንጂ የሠራ
ተኛው መደብ ድርጅት ፓርቲው ብቻ አይደለም ።
ወዝአደሩ በካፒታል ላይ የተሳካ ትግል ለማካሄድ
እንዲያስችለው ሌሎችም በዛ ያሉ ድርጅቶች አሉት ።
እነሱም የሙያ ማህበሮች ፡ የህብረት ሥራ ድርጅቶች ፡
የፋብሪካ ድርጅቶች ፡ የፓርላማ ቡድኖች ፡ የፓርቲ
አባል ያልሆኑ የሴቶች ድርጅቶች ፡ የዜና አገልግሎት ፡
የባህልና ትምህርታዊ ድርጅቶች ፡ የወጣቶች ድርጅ
ቶች ፡ አብዮታዊ ታጋይ ድርጅቶች ፡ (በግልጽ አብዮታዊ
ድርጊት ጊዜ) እንደ መንግሥት ድርጅት ቅርፅ ዓይ
ነት የተወካዮች ሶቪየቶች) (ማለትም ወዝአደሩ በሥል
ጣን ላይ ካለ). . .ወዘተ. ። ከእነዚህ ድርጅቶች ውስጥ
እጅግ አብዛኛዎቹ የፓርቲው አይደሉም ፤ ከእነዚህ
ውስጥ ጥቂቶቹ ብቻ ከፓርቲው በቀጥታ ይያያዛሉ
ወይንም የእሱን ቅርንጫፍ ይመሠርታሉ ። እነዚህ ሁሉ
ድርጅቶች በተወሰኑ ሁኔታዎች ስር ለሠራተኛው
መደብ ፍጹም አስፈላጊ ናቸው ። ምክንያቱም ያለእነሱ
በትግሉ ልዩ ልዩ መልክ የወዝአደሩን የመደብ አቋም
ማጠናከር የማይቻል ይሆናል ። ምክንያቱም ያለእነሱ
ተልእኮው የቡርዧውን ሥርዓት በሶሻሊስት ሥርዓት መተ
ካት የሆነውን ወዝአደር ጠንካራ ለማድረግ የማይቻል
ይሆናል ። ነገር ግን ድርጅቶች እንደዚህ እየበዙ እንዴት
አንድ ብቻ የሆነ የመሪነት ተግባር ለማስፈጸም ይቻላል?
የእነዚህ ድርጅቶች መብዛት የመሪነትን መለያየት
ላለማስከተሉ ምን ዋስትና አለ? እነዚህ ድርጅቶች እያ



ንዳንዳቸው በየራሳቸው ልዩ መስክ ሥራቸውን ያካሂ
ዳሉ ፡ ስለሆነም እርስ በርስ እንቅፋት ሊሆኑ አይችሉም?
ሊባል ይችል ይሆናል ። ይህ መቼም እውነት ነው ።
ነገር ግን በዚህም ላይ ሌላ እውነት አለ ። እነዚህ ሁሉ
ድርጅቶች አንድን መደብ ፡ የወዝአደሩን መደብ ስለሚ
ያገለግሉ በአንድ አቅጣጫ መሥራት አለባቸው ። እን
ግዲህ የሚከተለው ጥያቄ ይነሳል ። የእነዚህ ሁሉ ድር
ጅቶች ሥራ የሚመራበትን መስመር ፡ አጠቃላዩን አቅ
ጣጫ የሚወስነው ማነው? አስፈላጊው ልምምድ ኖሮት
እንደዚህ ያለውን አጠቃላይ መስመር ሊሠራ የሚያቅድ
ብቻ ሳይሆን በተጨማሪም በቂ የሆነ ተሰሚነት ኖሮት
የአመራር አንድነትን ለማስገኘትና እንቅፋት እንዳይ
ኖር እነዚህ ሁሉ ድርጅቶች ይህን መስመር እንዲከተሉ
ለማድረግ የሚችል ማዕከላዊ ድርጅት የት አለ? ይህ ድር
ጅት የወዝአደሩ ፓርቲ ነው ።

ፓርቲው ለእነዚህ አስፈላጊው ችሎታ ሁሉ
አለው ። ምክንያቱም መጀመሪያ የፓርቲው አባል ካል
ሆኑ የወዝአደሩ ድርጅቶች ጋር ቀጥተኛ ግንኙነት ያላ
ቸውና ብዙውንም ጊዜ የሚመሯቸው ምርጥ የሆኑ የወዝ
አደሩ መደብ ክፍሎች የሚሰበሰቡበት ማዕከላዊ ሥፍራ
ነው ። ሁለተኛም የሠራተኛው መደብ ምርጥ አባሎች
የሚሰበሰቡበት ማዕከላዊ ሥፍራ በመሆኑ የመደባቸ
ውን ማንኛውንም ድርጅት ለመምራት ብቁ የሆኑ የሠ
ራተኛውን መደብ መሪዎች ለማሠልጠን ወደር የሌለው
ት/ቤት ነው ። ሶስተኛ ፓርቲው የሠራተኛ መደብ መሪ
ዎችን በማሠልጠን ረገድ ወደር የማይገኝለት ት/ቤት
በመሆኑ ፡ ከልምምዱና ካለው ተሰሚነት የተነሳ የወዝ
አደሩን ትግል ሰብስቦ አንድ ማዕከላዊ አቋም ለመስ
ጠት የሚችል ድርጅት እሱ ብቻ ነው ። በዚህም ረገድ
የፓርቲው ያልሆነውን ማንኛውንም የሠራተኛውን

መደብ ድርጅት ፓርቲውን ከመደቡ ጋር ወደሚያገናኝ ወደ ተቀጥላ አካልና አስተላላፊ መቀነት ይለውጠዋል ።

ፓርቲው የወዝአደሩ የመደብ ድርጅት ከፍተኛው ቅርጽ ነው ። ይህ ማለት ደግሞ የፓርቲው ያልሆኑ ድርጅች ፤ የሙያ ማህበሮች ፤ የህብረት ሥራ ድርጅቶች. . .ወዘተ. በግልጽ (ይፋ) በፓርቲው አመራር ስር የበታች (ተገዥ) ሆነው ይግቡ ማለት አይደለም ። ነገሩ የሚለው በእነዚህ ድርጅቶች ውስጥ ያሉና ያለጥርጥርም በድርጅቶቹ ውስጥ ተደማጭነት ያላቸው የፓርቲው አባል የሆኑት ሰዎች እነዚህ የፓርቲው ያልሆኑ ድርጅቶች በሥራቸው ወደ ወዝአደሩ ፓርቲ ይበልጥ እንዲጠጉና በፈቃዳቸውም የእሱን አመራር እንዲቀበሉ ለማድረግ የተቻላቸውን ሁሉ ያደርጋሉ ነው ።

ስለዚህ ነው ሌኒን ፓርቲው የፖለቲካ መሪነቱ ወደ ማንኛውም የወዝአደሩ ድርጅት መዳረስ ያለበት «የወዝአደሩ መደብ ማኅበር ከፍተኛው ቅርጽ» ነው የሚለው ቅጽ ፴፩ ፤ ገጽ ፻፺፩ ይመልከቱ ።

ከፓርቲው የተለዩ ፤ ነፃ የሆኑ የፓርላማ አባሎችና ጋዜጠኞች ፤ ጠባብ አስተያየት ያላቸው የሙያ ማህበር መሪዎችንና መደዴ የሆኑ የህብረት ሥራ ማህበር ባለሥልጣኖችን የሚያፈራው የአድርባዮች» «ነፃ የመሆንና» «የገለልተኛነት» ቲዎሪ ከሌኒኒዝም ቲዎሪና ተግባር ጋር ፍጹም የማይገጥመው ስለዚህ ነው ።

፬. ፓርቲው የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት መሳሪያ ስለመሆን ፤ ፓርቲው የወዝአደሩ ድርጅት ከፍተኛው ቅርፅ ነው ። በወዝአደሩ መደብ ውስጥና በዚያ መደብ ድርጅቶች መሀከል ፓርቲው ተቀዳሚው መሪ ሀይል ነው ። ነገር ግን በምንም ዓይነት ከዚህ ተነስቶ ፓርቲው ራሱ



የመጨረሻው ግብ እንደሆነ ፤ ራሱ ለራሱ በቂ ሀይል እንደሆነ አድርጎ ለመቁጠር ይቻላል ማለት አይደለም ። ፓርቲው በወዝአደሩ መደብ ማህበር ከፍተኛው ቅርፅ ብቻ አይደለም ። በተጨማሪም የበላይ ገዥነቱ ገና ያልተገኘ ከሆነ የበላይ ገዥነቱን ለማግኘት ፤ የበላይ ገዥነቱ በተገኘ ጊዜ ደግሞ እሱን ለማጠናከርና ለማስፋፋት በወዝአደሩ እጅ ያለ መሳሪያ ነው ። ወዝአደሩ የሥልጣን ጥያቄ ጉዳይ ባይገጥመው ኖሮ ፤ የኢምፔሪያሊዝም ሁኔታ ፤ የጦርነቶች ግዴታነትና የቀውሶች መኖር የወዝአደሩን ሀይሎች በሙሉ ባንድ ቦታ መከማቸት ባይጠይቅ ኖሮ ፤ ቡርዧውን ለመገልበጥና የወዝአደሩን የበላይ ገዥነት ለማግኘት የአብዮታዊ እንቅስቃሴ ድሮችን በሙሉ ባንድ ላይ መሰብሰብ ባይጠይቅ ኖሮ ፓርቲው በሚሰጠው ግምት ይህን ያህልም ከፍ ባላለና በተቀሩት በወዝአደሩ ድርጅቶች ላይ በሙሉ ተጽእኖውን ለማድረግ ባልቻለ ነበር ። ወዝአደሩ በመጀመሪያ ፓርቲውን የሚፈልግው ለጠቅላይ መምሪያነት ነው ። ሥልጣንን በተሳካ አኳኋን ለመያዝ የግዴታ ይህ ሊኖረው ይገባል ። የወዝአደሩን ሰፊ ድርጅቶች በራሱ አካባቢ ለማሰለፍና ትግሉ እየተራመደ በሚሄድበት ጊዜ የጠቅላላውን እንቅስቃሴ አመራር ማእከላዊ ለማድረግ የሚችል ፓርቲ ሳይኖረው በሩሲያ ውስጥ የነበረው ወዝአደር አብዮታዊ የበላይ ገዥነቱን ሊመሠርት አይችል እንደነበረ እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ።

ነገር ግን ወዝአደሩ ፓርቲውን የሚፈልገው የበላይ ገዥነቱን ለማግኘት ብቻ አይደለም ። ይበልጥ የሚፈልገው የሶሻሊዝምን ፍጹም የሆነ ድል ለማግኘት የበላይ ገዥነቱንም ይዞ ለመቆየት ፤ ለማጠናከርና ለማስፋፋት ነው ።

«እጅግ ጥብቅና በእውነት ጠንካራ የሆነ ዲስፕሊን በፓርቲያችን ውስጥ ባይኖር ኖሮና እንዲሁም በሰፊው ሠራተኛ መደብ በሙሉ ፣ ማለትም በመላው በሚያስቡ ፣ ታማኝ በሆኑ ፣ ራሳቸውን አሳልፈው በሚሰጡ ፣ ተሰሚነት ባላቸውና ሊመሩ ወይንም ወደኋላ የቀረውን ክፍል ከራሳቸው ጋር ለማስተካከል ችሎታ ባላቸው ክፍሎች የተሟላና ያልተቆጠበ ድጋፍ ባያገኝ ኖሮ ቦልሼቪኮች ለሁለት ዓመት ተኩል ይቅርና ለሁለት ወር ተኩልም ቢሆን ራሳቸውን በሥልጣን ላይ ለማቆየት አይችሉ እንደነበር አሁን በእርግጥ ማንኛውም ሰው ይገነዘበዋል ። «(ቅጽ ፴፩ ፡ ገጽ ፩፻፳፫ ይመልከቱ ።)

አሁን የበላይ ገዥነቱን «ይዞ ማቆየትና» ፣ «ማስፋፋት» ማለት ምን ማለት ነው? በሚሊዮን የሚቆጠሩ ወዝአደሮችን በዲስፕሊንና በድርጅት መንፈስ መጥመቅ ማለት ነው ። በሰፊው ወዝአደር መሀከል እንደ ሲሚንቶ አጥብቆ የሚያያዝ ሀይልና እንደ ነቀዝ ከሚቦረቡረው ከንኡስ ከበርቴ ክፍሎችና ከንኡስ ከበርቴ ጠባዮች የሚጠብቀው ግድብ መፍጠር ማለት ነው ። የንኡስ ከበርቴውን ክፍል እንደገና በማስተማርና እንደገና በማነፅ የወዝአደሩን የድርጅት አሠራር ማጠናከር ማለት ነው ። መደቦችን ለማጥፋትና ለሶሻሊስት ምርት ድርጅት ሁኔታዎችን ለማዘጋጀት እንደሚችል ሀይል አድርገው ራሳቸውን ለማስተማር በሚያደርጉት ጥረት ሰፊ ወዝአደሮችን መርዳት ማለት ነው ። ነገር ግን ከአንድነቱና ከዲስፕሊኑ የተነሣ ጠንካራ ከሆነው ከፓርቲው ጋር በስተቀር እነዚህን ሁሉ ለመፈጸም አይቻልም ።



«የወዝአደሩ የበላይገዥነት» ይላል ሌኒን ፣ «በአሮጌው ህብረተሰብ ሀይሎችና ልማዶች ላይ የሚደረግ ፣ በደምና ያለደም ፣ ሰላማዊና ሰላማዊ ባልሆነ ፣ ወታደራዊና ኢኮኖሚያዊ ፣ ትምህርታዊና የአስተዳደር . . ሞገደኛ የሆነ ትግል ነው ። በብዙ ሚሊዮን የሚቆጠሩ ሰዎች ልማድ ሀይል እጅግ አስፈሪ የሆነ ሀይል ነው ። በትግል ከተፈተነ ከጠንካራ ፓርቲ በስተቀር ፣ በተሰጠው ክፍል ውስጥ ታማኝ ከሆኑት ሁሉ እምነት ከሚያገኝ ፓርቲ በስተቀር ፣ የሰፊውን ሕዝብ ስሜት ለማየትና ተጽእኖ (ኢንፍሉዌንስ) ለማድረግ ከሚችል ፓርቲ በስተቀር እንደዚህ ያለውን ትግል በተሳካ አኳኋን ለመምራት አይቻልም ። » (ቅጽ ፴፩ ፡ ገጽ ፳፯ ይመልከቱ ።)

ወዝአደሩ ፓርቲውን የሚፈልገው የበላይ ገዥነቱን ለማግኘትና ለማቆየት ነው ። ፓርቲው የወዝአደሩ የበላይ ገዥነት መሳሪያ ነው ።

፭. <u>ፓርቲው የፍላጎቶች አንድነት ያለበት ፣ ከአንጃዎች (ፋክሽናል) መኖር ጋር የማይገጥም አንድነት ስለመሆኑ</u> ፣ ከአንድነቱና ከጠንካራ ዲሲፕሊኑ የተነሳ ጠንካራ ከሆነ ፓርቲ ሌላ የወዝአደሩን የበላይ ገዥነት ማግኘትና ይዞ ለመቆየት አይቻልም ። የፓርቲው አባሎች በሆኑት በኩል የፍላጎት አንድነት ከሌላ ፣ የተሟላና ፍጹም የሆነ የተግባር አንድነት ከሌለ ፣ በፓርቲው ውስጥ ጠንካራ ዲሲፕሊን መኖሩ የማይታሰብ ነገር ነው ። መቼም ይህን ማለት በፓርቲው ውስጥ የሃሳብ ግጭት ሊኖር መቻሉ በዚሁ አማካይነት ይከለከላል

ወይንም ይታገዳል ማለት አይደለም ። እንዲያውም በተቃራኒ ጠንካራ ዲሲፕሊን በፓርቲው ውስጥ ወቀሳና የሃሳብ ግጭት ሊኖር እንደሚችል አድርጎ ይቆጠራል እንጂ አያስወግድም ። እንዲያው ዲሲፕሊን ሲባል «እውር» መሆን አለበት ማለት ነው? አይደለም ፣ እንዲያውም በተቃራኒ ጠንካራ ዲሲፕሊን አውቆና በገዛ ፈቃድ የሌላን ሃሳብ መቀበል ሊኖር እንደሚችል ነገር አድርጎ ይቆጥራል እንጂ አያስወግድም ። ምክንያቱም ከንቃት የመጣ ዲስፕሊን ብቻ ነው በእርግጥ ጠንካራ ዲሲፕሊን ሊሆን የሚችለው ። ይሁን እንጂ የሃሳብ ግጭት ካበቃ በኋላ ፣ ወቀሳ እስከመጨረሻው ተካሂዶ ካለቀና ውሳኔ ላይ ከተደረሰ በኋላ የመላው ፓርቲ አባሎች የፍላጎት አንድነትና የተግባር አንድነት አስፈላጊ ሁኔታዎች ናቸው ። ያለእነዚህ ሁኔታዎች የፓርቲ አንድነትም ይሁን በፓርቲው ውስጥ ጠንካራ ዲሲፕሊን ሊኖር አይችልም ።

> «በአሁኑ ሀይለኛ የእርስ በርስ ጦርነት መጀመሪያ ዘመን ላይ ኮሚኒስት ፓርቲው ተግባሩን ሊያሟላ የሚችለው እጅግ ማእከላዊ በሆነ መንገድ የተደራጀ እንደሆነ ብቻ ፣ ወደ ሚሊታሪ ዲሲፕሊን የሚጠጋ ጠንካራ ዲሲፕሊን በውስጡ የሰፈነ እንደሆነና የፓርቲው ማዕከላዊ ሥፍራ ሰፊ ሥልጣን የያዘና የፓርቲው አባሎች ሁለንታዊ እምነት ያለው ሀይለኛና ተሰሚነት ያለው ልሳን የሆነ እንደሆነ ብቻ ነው ።» ይላል ሌኒን (ቅጽ ፴፩ ፣ ገጽ ፪፻፲፩—፪፻፲፪ ይመልከቱ ።)

ከበላይገዥነቱ መገኘት ቀደም ብሎ ባለው የትግል ጊዜ በፓርቲው ውስጥ ዲሲፕሊንን በሚመለከት ረገድ ያለው አቋም ይህ ነው ።



የበላይገዥነት ከተገኘ በኋላ በፓርቲው ውስጥ ስላለው ዲሲፕሊን ተመሳሳይ የሆነ አባባል ግን ይበልጥ ከፍ ባለ ደረጃ ሊባል ይገባል ።

> «ማንም» ይላል ሌኒን ፣ «ማንም የወዝአደሩን ፓርቲ ጠንካራ ዲሲፕሊን ትንሽ እንኳን የሚያዳክም (በተለይም በበላይገዢነቱ ጊዜ) በርግጥ በወዝአደሩ ላይ ቡርዧውን ያግዛል ። (ቅጽ ፴፩ ፣ ገጽ ፩፻፫ ይመልከቱ ።)

ከዚህ ለመረዳት የሚቻለው የአንጃዎች መኖር ከፓርቲው አንድነት ጋርም ይሁን ከጠንካራ ዲሲፕሊን ጋር የሚጣጣም አይደለም ። የአንጃዎች መኖር ወደ ብዙ ማዕከላዊ ሥፍራዎች መኖር እንደሚያመራና የብዙ ማእከላዊ ሥፍራዎችም መኖር ማለት በፓርቲው ውስጥ አንድ የጋራ የሆነ ማእከላዊ ሥፍራ መጥፋት ፣ የፍላጎት ፣ አንድነት መከፋፈል ፣ የዲስፕሊን መዳከምና መበታተን ፣ የበላይገገርነቱ መዳከምና መበታተን ማለት እንደሆነ እስከዚህም ማረጋገጫ አያስፈልገውም ። አዎን ፣ የወዝአደሩን የበላይገገርነት በመቃወም የሚታገሉትና ወዝአደሩን ወደ ሥልጣን ለመምራት ምንም ፍላጎት ያልነበራቸው የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች እንደ የአንጃዎችን መኖር ነፃነት ያለውን ግድየለሽነት (ሊብራሊዝም) ሊፈቅዱ ይችላሉ ። ምክንያቱም ጠንካራ ዲስፕሊን ምንም አያስፈልጋቸውምና ነው ። ነገር ግን የወዝአደሩን የበላይ ገዢነት በማግኘትና በማጠናከር ድርጊታቸው የሚመራው የኮሚኒስት ኢንተርናሽናል ፓርቲዎች «ሊበራል» ለመሆን ወይንም የአንጃዎችን መኖር ነፃነት ለመፍቀድ አይችሉም ።

ፓርቲው የፍላጎት አንድነትን ያሳያል ፣ ይህም ሁሉንም ዓይነት አንጃነትንና በፓርቲው ውስጥ የተሰሚነት ሀይል መከፋፈልን ያስወግዳል ።

ከዚህ የተነሳ «ከፓርቲው አንድነትና ለወዝአደሩ የበላይገዥነት መሳካት የወዝአደሩን ግንባርቀደም የፍላጎት አንድነት ማግኘቱ እንደ መሠረታዊ ሁኔታ የመሆኑን እንፃር በማየት» ሌኒን የአንጃነትን አደጋ አስጠነቀቀ ፡ ይህም «ስለፓርቲ አንድነት» የ፲ኛ ፓርቲ ባደረገው አስረኛው ጉባኤ ልዩ ውሳኔ ውስጥ ተደ ሆአል ።

ከዚህ የተነሳ «ሁሉም አንጃነት በፍጹም እንዲ ጠፉና «በተለያዩ መድረክ መሠረት ላይ ተቋቁመው የነበሩት «ቡድኖች በሙሉ በፍጥነት እንዲበታተኑ» ይህን ካላደረጉ «ያለምንም ጥያቄ በፍጥነት ከፓርቲው እንዲወገዱ» በማለት ሌኒን ጠየቀ ። («ስለፓርቲያችን አንድነት» የተላለፈውን ውሳኔ ተመልከት ።)

፮. ፓርቲው ከአድርባይ ክፍሎች ራሱን በማን ፃት ጠንካራ ይሆናል ። በፓርቲው ውስጥ የአንጃነት ምንጩ ያለው ከአድርባይ ክፍሎቹ ነው ። ወዝአደሩ ተነጥሎ ብቻኛ የሆነ መደብ አይደለም ። በካፒታሊዝም እድገት ስር ወዝአደር በሚሆኑ ቁጥራቸው ብዙ በሆነ ገበሬዎች ፡ ንኡስ ከበርቴዎችና ምሁራን እንደገና በየጊዜው የሚሞላ ነው ። በዚህን ጊዜም የወዝአደሩ ላይኛው ክፍል የሆኑት ከቅኝ ግዛቶች ከሚጨምቀው እጅግ ከፍተኛ ትርፍ በቡርዧ የሚቀለቡት የሙያ ማህበር መሪ ዎችና የፓርላማ አባሎች በመበስበስ ሂደት ውስጥ ናቸው ። «እነዚህ ቡርዧ የሆኑ ሠራተኞች ወይንም 'የወዝ መሳፍንት' ክፍል ፡» ይላል ሌኒን ፡ «በአኗኗር ስልታቸው ፡ በገቢያቸው መጠንና በጠቅላላ ርእዮታ ቸው መደዴ የሆኑት የሁለተኛው ኢንተርናሽናል ዋና ድጋፍ ነበሩ ። በ፲ኛ ጊዜ ደግሞ የቡርዧ ዋና ህብረተሰ



ባዊ ድጋፍ ናቸው ። ምክንያቱም በሠራተኛው መደብ እንቅስቃሴ ውስጥ የቡርዧው እውነተኛ ወኪል (ሰላይ) የካፒታሊስት መደብ የወዝ (ሥራ) መቶ አለቆች (ሌበር ሊዩቱነንትስ) . . . የጥገናዊነትና የትምክህተኛነት እውነተኛ ድልድይ ናቸውና ።» (ቅጽ ፲፱ ፡ ገጽ ፷፯ ይመልከቱ ።)

እነዚህ ሁሉ የንኡስ ከበርቴ ቡድኖች በልዩ ልዩ መንገድ በፓርቲው ውስጥ ሠርገው በመግባት የማመንታትንና የአድርባይነትን መንፈስ ፡ የሞራል ውድቀትንና እርግጠኛ ያለመሆንን መንፈስ ያስገቡበታል ። የአንጃነትንና የመበታተንን ምንጭ የሚይዙ ፡ ከውስጥ በመሆን ፓርቲውን ሥርዓት የሚያሳጡና የሚበጠብጡ ከሁሉም እነሱ ናቸው ። እንደዚህ ያሉት «ደጋፊዎች» ከጀርባ አድርጎ ከኢምፔሪያሊዝም ጋር መዋጋት ማለት ራስን በሁለት እሳት መሀከል ፡ ከፊትና ከኋላ ማስጠመድ ማለት ነው ። ስለሆነም በኢምፔሪያሊዝም ላይ የተሳካ ትግል ለማካሄድ እንደዚህ ባሉት ላይ ርህራሄ የሌለው ትግል ማድረግ ፡ ከፓርቲው ማባረር በቅድሚያ አስፈላጊ የሚሆን ነገር ነው ።

በፓርቲው ውስጥ ሆኖ አድርባዮችን በርእዮተ ዓለም ትግል «የማሸነፍ» ቲዎሪ ፡ በአንድ ነጠላ ፓርቲ ክልል ውስጥ እነዚህን ክፍሎች «የማሸነፍ» ቲዎሪ የበሰበሰና አደገኛ የሆነ ቲዎሪ ነው። ይህም ፓርቲውን ወደ ሽመድማዳነትና የዘወትር ደካማነት ስጋት ላይ የሚጥል ፡ ፓርቲውን የአድርባዮች መፈንጫ ወደማድረግ ስጋት ላይ የሚጥል ፡ ወዝአደሩ ያለአብዮታዊ ፓርቲ የማስቀረት ስጋት ላይ የሚጥል ፡ ወዝአደሩ ከኢምፔሪያሊዝም ጋር በሚያደርገው ትግል ዋና መሳሪያውን የመከልከል ስጋት ላይ የሚጥል ነው ። እንደ ማርቶቭና

ዳን ፣ እንደ ፓትሰብሽና አክሲልሮድ ያሉትን ሰዎች በውስጡ ቢይዝ ኖሮ ፓርቲያችን ወደ አደባባይ ሊወጣ አይችልም ነበር ፣ ሥልጣንን ለመያዝና የወዝአደሩን የበላይገዥነት ለማደራጀት አይችልም ነበር ። በእርስ በርሱ ጦርነት አሸናፊ ሆኖ አይወጣም ነበር ። ፓርቲያችን ውስጣዊ አንድነትንና ወደር የሌለው መሳሳብን ሊያገኝ የቻለው ከሁሉም በደህና ጊዜ ከአድርባይነት ብከላ ራሱን ሊያነፃ በመቻሉ ነበር ። ምክንያቱም ሜንሼቢኮችንና አሟሻሽ ኃይሎችን (ሊኪዊዴተርስ) ከውስጡ ሊያስወግድ በመቻሉ ነበር ። የወዝአደሩ ፓርቲዎች የሚያድጉትና ጠንካራ የሚሆኑት ከአድርባዮችና ጠጋኞች ፣ ከሶሻል ኢምፔሪያሊስቶችና ከሶሻል ትምክህተኞች ፣ ከሶሻል አርበኞችና ሶሻል ፓሲፍስቶች ራሳቸውን በማንፃት ነው ።

ፓርቲው ከራሱ ውስጥ አድር ባይ ክፍሎችን አውጥቶ ራሱን በማንፃት ነው ጠንካራ የሚሆነው ።

> «በኛ ውስጥ» ይላል ሌኒን «በኛ ውስጥ ጠጋኞችና ሜንሼቪኮች እያሉ በወዝአደሩ አብዮት አሸናፊ መሆን ፍጹም አይቻልም ፤ እሱንም መደገፍ አይቻልም ። ይህ በመርህ ግልጽ ነው ። በሩሲያና በሁንጋሪ ልምድም በሚያስደንቅ ሁናቴ ተረጋግጦአል ። ሜንሼቪኮች ፣ ጠጋኞችና ንኡስ ከበርቴ ዲሞክራቶች በፓርቲያችን ውስጥ ቀርተው ቢሆን ኖሮ የሶቭየት አገዛዝ ያለጥርጥር ይገለበጥ የነበረበት አስቸጋሪ ሁናቴ በሩሲያ ውስጥ ብዙ ጊዜ እንደተነሳ ይታወቃል ።. . ብዙውን ጊዜ እንደሚታመነው በኢጣሊያን ውስጥ ሥልጣንን ለመያዝ በወዝአደሩና በቡርዧው መሀከል ወሳኝ የሆኑ ውጊያዎች በቅርቡ መካሄዳቸው የማይቀር ነው ። በእንደዚህ ያለ ጊዜ ከፓርቲው ውስጥ ሜንሼቢኮችን ፣ ጠጋኞችን ፣ ቱራቲስቶችን ማስወገድ አስፈላጊ ብቻ ሳይሆን ሊያወላውሉ የሚችሉትን ፣ ከጠጋኞች ጋር ወደ «አንድነት» ለማዘንበል የማመንታት አዝማሚያ የሚያሳዩትን እጅግ ግሩም የሆኑ ኮሚኒስቶችን እንኳን ቢሆን ማስወገዱ ፣ ከሁሉም ኃላፊነት ያለበት ቦታ መንሳቱ ጠቃሚ ሊሆን ይችላል ።. . . በአብዮቱ ዋዜማ ጊዜ ፣ ለድሉም እጅግ ከፍተኛ የሆነ ትግል በመካሄድ ላይ ባለበት ጊዜ በፓርቲው የኃላፊነት ቦታ ትንሽ እንኳን ማመንታት ሁሉንም ነገር ሊያፈራርስ ፣ አብዮቱን ሊያጨናግፍ ፣ ሥልጣኑን ከወዝአደሩ እጅ ሊያስነጥቅ ይችላል ። ምክንያቱም ይህ ሥልጣን አልተጠናከረም ። ምክንያቱም በእሱ ላይ ያለው ተቃውሞ አሁንም ገና ጠንካራ ነው ። እንደዚህ ባለው ጊዜ የሚያወላውሉ መሪዎች ለቀው መውጣታቸው ፓርቲውን ፣ የሠራተኛውን መደብ እንቅስቃሴ አብዮቱን ያጠናክረዋል እንጂ አያዳክመውም ። » (ቅጽ ፳፭ ፣ ገጽ ፬፻፳፱ ፣ ፬፻፳፫ ፣ ፬፻፳፬ ይመልከቱ ።)



## ፱. የሥራ ሥልት (ስታይል)

የሥነ ጽሑፍን ሥልት ማስመልከቱ አይደለም ። በሃሳቢ ያለው የሥራ ሥልት ነው ። እሱም ሌኒኒዝም በተግባር ላይ ሲውል ልዩ ዓይነት ሌኒኒስት ሠራተኛን የሚፈጥረውን ያን የተወሰነና ልዩ የሆነ ባህርይ ነው ።

ሌኒኒዝም በሥራ ላይ ልዩ የሌኒኒስት ሥልትን የሚፈ
ጥር የቲዎሪና የተግባር ትምህርት ቤት ነው ።

የዚህ ሥልት መለያ ባህርይዎች ምንድን ናቸው?
ልዩ ጠባዮቹ ምንድን ናቸው?

ሁለት የተወሰኑ ባህርይዎች (መልኮች) አሉት ።

ሀ/ የሩሲያ አብዮታዊ ፈጣን ጉዞና (ስዊፕ)

ለ/ የአሜሪካ የሥራ ብቁነት (ኢፊሸንሲ)

የሌኒኒዝም ሥልት እነዚህን ሁለቱን የተወሰኑ
ባህርይዎች በፓርቲውና በመንግሥት ሥራ ውስጥ
ማዋሀድን ይይዛል ።

የሩሲያ አብዮታዊ ፈጣን ጉዞ ለውዝፍነት ፣ ለሰ
ልቺ ለሆነ ተደጋጋሚ ሥራ ፣ ለወግ አጥባቂነት ፣ ለአእ
ምሮ መሻገትና ለጥንታዊ ባህል ወራዳ ምርኮኛነት
ፍቱን የሆነ ማርከሻ መድሀኒት ነው ። የሩሲያ አብዮታዊ
ፈጣን ጉዞ ሃሳብን የሚያነቃቃ ፣ ነገሮችን ወደፊት የሚ
ገፋፋ ፣ ያለፈውን ጊዜ በመስበር አዲስ አመለካከት
የሚከፍት ሕይወት ሰጭ የሆነ ሀይል ነው ። ያለእሱ
ምንም ዓይነት የእድገት እርምጃ አይቻልም ።

ነገር ግን የሩሲያ አብዮታዊ ፈጣን ጉዞ ከአሜሪ
ካን የሥራ ብቁነት ጋር ካልተዋሀደ በስተቀር በተግባር
ወደ ባዶ «አብዮታዊ» ማኒሎቪዝምነት የመዋረድ
ወይንም ዝቅ የማለት ዕድል ያጋጥመዋል ። የዚህ ዓይ
ነቱ የመዋረድ ምሳሌዎች በጣም ብዙ ናቸው ። የአዋጅ
ሀይል ማንኛውንም ነገር ሊያስተካክልና ማንኛውንም
ነገር እንደገና ለመሥራት ይችላል ከሚል እምነት የሚ
መነጨው «አብዮታዊ» የሥራ እቅድ የማርቀቅንና
«አብዮታዊ» እቅድ የመንደፍን በሽታ የማያውቅ ማነው



እሱ? አይ አህረንበርግ የተባለ የሩሲያ ፀሐፊ ዘ. ፐርኮ
ማን (ፍጹም የሆነው የኮሚኒስት ሰው) በተሰኘው ታሪኩ
ውስጥ በዚህ በሽታ የተለከፈውን ዓይነት «ቦልሼቪክ»
አሳይቷል ። ይህም «ቦልሼቪክ» ፍጹም የሆነ ፣ እንከን
የማይወጣለት ሰው ለማግኘት ፎርሙላ የመፈለግ ተግ
ባር ለማካሄድ ተነስቶ. . .በዚህ «ሥራ እንደተዋጠ»
ያሳያል ። ታሪኩ ትልቅ ማጋነን አለበት ። ይሁን እንጂ
በእርግጥ ትክክለኛ የሆነ የበሽታውን ተመሳሳይ መልክ
ይሰጣል ። ነገር ግን እኔ እንደማስበው ፣ በዚህ በሽታ
የተያዙትን ሰዎች ከሌኒን የበለጠ ያለርህራሄና በመረረ
አኳኋን ያቃቂላቸው የለም ። ሌኒን ይህን የሥራ እቅድ
የመቀመምና አዋጆች የማውጣት ጤነኛ ያልሆነ እም
ነት ክፉኛ ሲወርፈው «የኮሚኒስት ተንጎራዳጅ» ብሎ
ታል ።

«ኮሚኒስት ተንጎራዳጅ ማለት የኮሚኒስት
ፓርቲው አባል የሆነና ገና ከውስጡ ያል
ተመነጠረ ሲሆን ኮሚኒስት አዋጆችን በማው
ጣት ለችግሮቹ ሁሉ መፍትሄ የሚያስገኝላ
ቸው አድርጎ የሚያስብ ሰው ነው ። (ቅጽ ፳፯፣
ገጽ ፺—፺፩ ይመልከቱ ።)

ሌኒን ብዙ ጊዜ የውስጠ ባዶ «አብዮታዊ»
ሐረጎች ጥራዝ ነጠቅነትን ግልጽ ከሆነ የቀን ተቀን
ሥራ ጋር ያነፃፅራል ። በዚህም ሁናቴ «አብዮታዊ»
የሥራ እቅድ ቅመማ ለእውነተኛ ሌኒኒዝም ስምና መን
ፈስ አስፀያፊ እንደሆነ በአንክሮ ያሳያል ።

«አነስ ያሉ ጉረኛ የሆኑ ባለግርማ ሐረጎች ፣ ግን
በዛ ያለ የቀን ተቀን ሥራ. . .» ይላል ሌኒን ። «አነስ
ያለ የፖለቲካ ርችት ፣ ግን በጣም ቀላል ፣ ነገር ግን እጅግ

ጠቃሚ ለሆነው . . .ኮሚኒዝምን ለመገንባት ሀቅ የበለጠ ግምት መስጠትና ማጤን ።. . .» (ቅጽ ፳፱ ፣ ገጽ ፫፻፺፩—፱፺፭)

ለአብዮታዊ ማኒሎቪዝምንትና ለዕፀብ ድንቅ የሥራ እቅድ ቅመማ አሜሪካዊ የሥራ ብቁነት (ብቃት) ፍቱን የሆነ ማርከሻ መድሀኒት መሆኑን አጣምሮ ማየት ይቻላል ። የአሜሪካን የሥራ ብቁነት ፣ ያ የማይበገር ፤ እንቅፋትን የማያውቅና የማይቀበል ሀይል ነው ። «ያ ፣ በዚያ ሥርዓት ተከታይ በሆነው ፤ ተስፋ በማይቆርጥ ችሎታው ሁሉን ዓይነት እንቅፋቶች ወዲያ የሚጠራርጋቸው ፣ ያ ፣ አነስተኛ ቢሆንም እንኳን አንዴ የተጀመረው ተግባር እስኪያልቅ ድረስ የሚቀጥልና ያለ እሱም ከፍተኛ የሆነ ጠቃሚ ሥራ መሥራት የማይቻል የሚሆነው ሀይል ነው ።

ነገር ግን የአሜሪካን የሥራ ብቁነት ከሩሲያ አብዮታዊ ፈጣን ጉዞ ጋር ካልተዋሀደ ወደ ጠባብና ዓላማቢስ ተግባራዊነት የመዋረድ ዕድል ያጋጥመዋል ። ያንን አልፎ አልፎ አንዳንድ «ቦልሼቪኮች» እንዲዋረዱና የአብዮቱን ዓላማ እንዲተዉ ያደረጋቸውን የጠባብ ኢምፕሪሲዝምና የዓላማ ቢስ ተግባራዊነትን በሽታ ያልሰማ ማን ነው? የዚህን ልዩ ዓይነት የሆነ በሽታ ነፀብራቅ እርቃኑን የቀረ ዓመት በሚል ርዕስ ቢ. ፕልኒያክ በጻፈው ታሪክ ውስጥ እናገኛለን ። ይህም ታሪክ የሚያሳየው ጠንካራ ፍላጎትና ተግባራዊ ቁርጠኛነት ያላቸውን «ቦልሼቪኮች» ግን ያለ አንዳች የወደፊት ዓላማ «ነገሩ ስለምን እንደሆነ» ምንም ሳያውቁ ፣ «በሀይል» የሚሠሩትን ፣ ስለሆነም አብዮታዊውን የሥራ ጎዳና ስተው የሚባዝኑትን ነው ። ይህንን የተግባራዊነት በሽታ ከሌኒን የበለጠ ጠለቅ ባለ አኳኋን ያቃቁለ



የለም ። «የጠባብ አስተሳሰብ ኢምፕሪሲዝም» «የእእምሮ ቢስ ተግባራዊነት» ብሎ ሰይሞታል ። በመላው የቀን ተቀን ድርጊቶች ውስጥ የአብዮታዊ አመለካከት መኖርን አስፈላጊነት ከጠቃሚ የፖለቲካ ሥራ ጋር ብዙውን ጊዜ ያነፃፅር ነበር ። በዚህም ሁኔታ ይህ ዓላማ ቢስ ተግባራዊነት ልክ እንደ «አብዮታዊ» የሥራ እቅድ ቅመማ ለእውነተኛ ሌኒኒዝም አስፀያፊ መሆኑን በአንክሮ ያሳያል ። የሩሲያ አብዮታዊ ፈጣን ጉዞ ከአሜሪካን የሥራ ብቁነት ጋር መዋሀድ በፓርቲው ውስጥና በመንግሥት ሥራ የሌኒኒዝም መሠረተ ነገር ነው ።

ይህ መዋሀድ ብቻ ነው የተሟላ ዓይነት የኮሚኒስት ሠራተኛ ፣ በሥራ ውስጥ የሌኒኒዝምን ስልት የሚፈጥረው ።



1. (ስታሊን) የኔ አይታሊክስ
2. የ፲፱፻፭ አብዮት ይህም አብዮት ዱማ የተሰኘው የመጀመሪያው የሩሲያ ፓርላማ ከ፲፱፻፮—፲፱፻፲፯ ወደ መቋቋሙ አመራ ።
3. እዚህ ላይ የተመለከተው ከ፲፱፻፯—፲፱፻፲ ድረስ ያሉት ዓመታት ሲሆን ይህም በእስክራ (የእሳት ፍንጣቂ) በተሰኘው ጋዜጣ አዘጋጅ ቦርድ ውስጥ ሌኒን ተቀዳሚውን ሚና ይጫወት (ይዞ) የነበረ ጊዜ ነው ።
4. (ስታሊን) የኔ አይታሊክስ
5. (ስታሊን) የኔ አይታሊክስ
6. ከቦልሼቪክ አብዮት በፊት በነበሩት ዓመታት ትሮትስኪን («የቋሚ» ቲዮሪ አመንጪ ከሆኑት አንዱ ) ከነ ሌኒንና ስታሊን ጋር ከሚለዩት ዋና ዋና ነጥቦች ውስጥ አንዱ የትሮትስኪ የወዝ አደሩን አብዮት ከሰፊው ገበሬ ጋር ለማያያዝ ማመንታት ነበር ።
7. (ስታሊን) የኔ አይታሊክስ
8. በማዕከላዊ ቡልጋሪያ ውስጥ ያለ በባልካን ሀገሮች የሚአቋርጥ መተላለፊያ ። ይህም በ፲፰፻፸፯—፸፰ ሩሲያኖች ቱርኮችን ካሸነፉበት በስተደቡብ ያለ ነው ።
9. (ስታሊን) የኔ አይታሊክስ
10. (ስታሊን) የኔ አይታሊክስ
11. (ስታሊን) አይታሊክሶች በሙሉ የኔ ናቸው ።
12. (ስታሊን) የኔ አይታሊክስ
13. «ካዴት» ተብለው የሚጠሩት ህገመንግሥታዊ ዲሞክራቶች ናቸው ። ይህም የከተማ ፕሮፌሽናል ቡድኖች ተወካዮች የሆኑትን ለዘብተኞችን (ሊበራልስ) በገጠር ያሉትን ራሳቸውን የሚያስተዳድሩ ዜምስቶቮ የተሰኙትን ክፍሎች (ቦዲስ) የሚያጠቃልል ፓርቲ ነው ። «ካዴት» በ፲፱፻፭ አብዮት ጊዜ እጅግ ተሰሚነት የነበረውና ብቁ የነበረ ድርጅት ሲሆን በመጀመሪያ ዱማ አብዛኛውን መቀመጫ አሸንፏል ።
14. «የዱማ ጊዜ» ከሚያዝያ ፲፱፻፮ እስከ የካቲት ፲፱፻፲፯ አብዮት ጊዜ ያለው ሲሆን በዚህ አብዮት ጊዜ ከዱማ ተወካዮች ውስጥ የሆነው ለዘብተኛ ቡድን የአብዮቱን መሪነት ይዞ የዛር ጻግማዊ

ኒኮላስን ከዙፋኑ ለቆ የመውረድ ስምምነት ድርድር በማድረግ ጊዜያዊውን መንግሥት አቋቋመ ። በእነዚህ ዓመታት ውስጥ (፲፱፻፮—፲፱፻፲፯) አራት ዱማዎች ነበሩ ።

15. የአራተኛው የመጨረሻው ዱማ ተወካይ የሆነው አሌክሳንደር ክሬንስኪ ከዛር ዳግማዊ ኒኮላስ ከዙፋን መውረድ በኋላ በተደ ራጀው የመጀመሪያው ጊዜያዊ መንግሥት ውስጥ አባል የነበረ ሲሆን አባል ለመሆን የበቃም ሶሻሊስት እሱ ብቻ ነበር ።ከፍ ትህ (ጀስቲስ) ምንስትርነት ወደ ጦር ምንስትርነት ከፍ ካለ በኋላ በሐምሌ ውስጥ የካቢኔው ዋና በመሆን ልዑል ልቮቮን ተካው ። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ እስከ ጥቅምት ቦልሼቪክ አብዮት ድረስ በሩሲያ ኦፊሲየል የሆነ የሀገር ውስጥና ኢንተርናሽናል መመሪያ ላይ ከፍተኛ ተፅእኖና የበላይነት ነበረው ።

16. ዲሞክራቲክ ጉባኤ የተሰኘው መሀል ቤት በሆኑ የግራ ክንፍ ቡድኖች መሀከል ድጋፉን ለማጠናከር ሲል ክሬንስኪ የጠራው ጉባኤ ነው ። እነዚህም ቡድኖች የተወከሉት በሁብረት ሥራ ድርጅቶች ፣ (ኰ ኦፐሬቲቭስ) በሙያ ማህበሮች ፣ በቀበሌ መንግሥት ተቋሞች ነው ። ጀኔራል ኮርኒሎቭ የክሬንስኪን መንግሥት ለመገልበጥ «የቀኝ ሙከራ ካደረገ በኋላ ክሬንስኪ በዚህ ሙከ ራው በከፍተኛ ፍጥነት እያደገ የነበረውን የቦልሼቪኮችን ከህ ዝብ ድጋፍ ማግኘት ለማደናቀፍና ለመቋቋም ተስፋ አድርጎ ነበር።

17. «ፓርላማ» የሚሰኘው ብዙውን ጊዜ ለሪፐብሊኩ ደርግ ይሰጥ የነበረ ስም ነው ። ይህ ደርግ ከመስከረሙ ዲሞክራቲክ ጉባኤ መዘጋት በኋላ በክሬንስኪ የተጠራ ሲሆን ዓላማውም በጊዜያ ዊው መንግሥትና ሊቋቋም በነበረው ሕዝባዊ (ኮንስቲቱወንት) ሸንጎ መሀከል ማገናኛ ድልድይ መሆን ነበር ። ሌኒን ቦልሼቪኮች በፓርላማው ውስጥ መሳተፋቸውን ክፉኛ የተቃወመው ቢሆ ንም በቦልሼቪኮች ፓርቲ ማዕከላዊ ኮሚቴ በድምፅ ብልጫ ተሸነፈ ። ይሁን እንጂ የቦልሼቪክ ልዑካን ከመጀመሪያው ስብ ሰባ በኋላ ለቀው ወጡ ። ከጥቅምቱ አብዮት በኋላ ቦልሼቪኮች እስኪተበትኑ ድረስ ፓርላማው መሰብሰቡን ቀጥሎ ነበር ።

18. አሁን ነጭ ሩሲያ በሆነው በብሬስት ቲቶቪስክ በመጋቢት ፫ ቀን ፲፱፻፲፰ ቦልሼቪኮች ከጀርመን ጋር እጅግ አሳፋሪና እጅግ ከባድ (ሎስትሊ) የሆነ ውል ተዋዋሉ ። ቦልሼቪኮች ወይ የገቡ ትን ቃል ኪዳን በመጠበቅ ጦርነቱን ለቀው መውጣት አለበለ ዚያም ከሥልጣን የመወገድን አደጋ መቀበል የሚኖርባቸው ጊዜ ነበር ። ዓላማቸውም ነበር ። ሁሉ በማያከራክር ሁኔታ ሩሲያ በፖላንድ ፣ በመገንዘብ በባልቲክ መንግሥታት ፣ በምስራቅ ፖላንድ ፣ በጆርጂያ ፣ በኡክሬይንና በሌሎችም ስፍራዎች ላይ ሩሲያ ያላ ትን ቁጥጥር ለመልቀቅና ለጀርመን ከፍተኛ የሆነ ካሣ ለመክ ፈል ሌኒን ፈቃደኛ ነበር ።



19. በሶስተኛው ዱማ ውስጥ ቦልሼቪኮች መሳተፋቸውን በመቃወም «የመመለስ» ወይንም «የአለመሳተፍ (ቦይኮት) ታክቲክ ያቀረ ቡት ቦልሼቪኮች ይህንን መመሪያ ሌኒን ህሳባዊና «የግራነት» ትግሮት በማለት በ፲፱፻፯ እና በ፲፱፻፰ ሲቃወመው በፓርቲው ውስጥ ብቻውን ነበር ለማለት ይቻላል ።

20. ይህ አባባል ሚኒሎቭ ከተሰኘው ስም የመጣ ሲሆን ይህም ስም የሞቱ ነፍሳት ከተሰኘው ከጎጎል መጽሐፍ ታሪክ የተገኘ ሲሆን የሚያሳየውም የዚህን ሰው መደዴነትና ፍሬቢስ የቀን ህልም አላሚነት ነው ።

21. እዚህ ላይ «ቡድን» (ጋንግ) የሚለው የሚያመለክተው አክሴ ልሮድ ፣ ማርቶቭ ፣ ፓትሬሶቭንና ሌሎችንም ነው ። እነዚህ በ፲፱፻፫ ሁለተኛው የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ ሌበር ፓርቲ ጉባኤ ላይ የሌኒንን ፕሮግራም የተቃወሙ ናቸው ።





